የጠላትን ይዞታ ለማስለቀቅና ለእንግሊዝ አስተዳደር ለማስረከብ ነው እንጂ፤ የኢትዮጵያን ጉዳይ የሚመለከት ኃላፊነት አልሰጠውም። መከራንና ችግርን የመመከት ኃይል ያላቸውና በቀላሉ የማይበገሩት ንጉሠ ነገሥትም፤ ትዕግሥታቸው ሰፊ ስለሆነ በደረሰባቸው ሁሉ ቅሬታቸውንና የሚሰማቸውን የኃዘን ስሜት ዊሊያም ፕላት እንዲያውቀው አልፈለጉም። ያደረጉት ጥረት ሁሉ፤ ከሁሉ አስቀድሞ ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ባለሥልጣኖች ጋር መልካምና የተግባባ ግንኙነት እንዲኖራቸው ስለሆነ፤ የሱዳን አገረገዥና የሱዳን ጦር አዛዥ ያደረሱባቸው በደል፤ ሞራላቸውን አላዳከመውም። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በዚህ በካርቱሙ ስብሰባ፤ አንቶኒ ኤደን ባደረገው ውሳኔ መሠረት በጉጃም በኩል ራሳቸው ለሚመሩት ጦር የተሟላ ትጥቅ እንዲዘጋጅላቸውና በቶሎ ዘመቻውን ለመጀመር በብርቱ ከተጨነቁበት ጉዳይ ሌላ እጅግ ያሳሰባቸው፤ ነፃነት ከተመለሰ በኋላ ከእንግሊዞች ጋር ስለሚኖራቸው ግንኙነት ነበር። ይህም ጉዳይ፤ ንግግር ሊደረግበትና ስምምነት ሊፈረምበት የሚችለው፤ ከጦርነቱ ፍጻሜ በኋላ እንጂ በጦርነቱ ወቅት መሆን እንደማይችል የታላቋ ብሪታንያ መሪዎች አስተያየት መሆኑን ጃንሆይ ቢያውቁትም፤ አንድ ውል እንዲደረግ ጥረታቸውን አላቋረጡም ነበር።

Reference: a/ FO-371-27516
b/ Antohony Mockler Haile Selassie's War

# ምዕራፍ ፭

## የንጉሠ ነገሥቱን ዘመቻ እንዲያዘጋጅ የተመረጠ መኮንን

### "ኦርድ ቻርል ዊንጌት"

በፋሽስት የተወረረችውን ኢትዮጵያን ነፃ ለማውጣት ለሚደረገው ጦርነት በካርቱም ስብሰባ ላይ በተወሰነው መሠረት፤ ሜጀር ኦርድ ቻርል ዊንጌት (Orde Charles Wingate) የተባለው እንግሊዛዊው የጦር መኮንን፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለሚመሩት ዘመቻ አዘጋጅና አማካሪያቸው እንዲሆን የታላቋ ብሪታንያ የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር ዋና አዛዥ ጄኔራል ኧርል ዌቨል መርጦ አቀረበው። የጦር ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን ለዚህ ኃላፊነት የተመረጠውን መኮንን ሹመት ከማጽደቁ በፊት፤ ስለሰውየው ታሪክና ችሎታ እንዲሁም ስለጠባዩና ስለ አቋሙ በዝርዝር ማወቅ አስፈልጎት ነበር።

እ.ኤ.አ የካቲት 26 ቀን 1903 ዓ.ም የተወለደው ኦርድ ዊንጌት የመጀመሪያና የሁለተኛ ደረጃ ትምህርቱን ከፈጸመ በኋላ፤ በእንግሊዝ አገር በታወቀው በወልዊች (Woolwich) በሚገኘው ሮያል ሚሊታሪ አካዳሚ የመድፈኛ መኮንን ሆኖ ተመረቀ። የዊንጌት ቤተሰቦች በአባቱም ሆነ በእናቱ በኩል ያሉት የውትድርና ሞያ የተማሩና ያገለገሉ ናቸው። ለምሳሌም ያህል፤ አባቱ ቻርል ዊንጌት በውትድርና ሞያው የአገልግሎት ዘመኑን ያሳለፈው በሕንድ በተቋቋመው የታላቋ ብሪታንያ ጦር ሠራዊት ውስጥ ሲሆን፤ የአባቱ አጎት ሰር ሬጂናልድ ዊንጌት ደግሞ፤ (Sir Reginald wingate) ከ1899 እስከ 1916 ዓ.ም ድረስ የሱዳን አገረገዥ ሆኖ ከሠራ በኋላ፤ ከዚያ ቀጥሎ ለሁለት ዓመታት በግብፅ የታላቋ ብሪታንያ ኮሚሽነር የነበረ ነው። ኦርድ ዊንጌትም በበኩሉ፤ በሚሊታሪ ሞያ ለመቀጠል የተቀረጠ ውሳኔ ያደረገው፤ ይህንን የቤተሰቡን ታሪክና ፈለግ በመከተል ነው እየተባለ ይነገርለታል።

እ.ኤ.አ በ1928 ዓ.ም ኦርድ ዊንጌት የሐያ አምስት ዓመት ወጣት መኮንን በነበረበት ጊዜ፤ በአባቱ አጎት በሰር ሬጂናልድ ዊንጌት ምክርና እርዳታ፤ ሱዳን ላይ በሚገኘው በእንግሊዝ የጦር ድርጅት ተዛውሮ፤ ሮዛይር እና ጋላባት በተባሉት ከኢትዮጵያ ጋር ለሚያዋስኑት ግዛቶች የፀጥታ ኃላፊ ሆኖ ተሾመ። በእነዚሁ ሁለቱን አገሮች፤ ሱዳንና ኢትዮጵያን በሚያካልሉት ጠረፎች ላይ፣ የሰውን ልጅ "ባሪያ" እያሉ በገንዘብ የሚሸጡትን ጨካኞችና እንዲሁም ዝሆኖችን እየጨፈጨፉ "የአሰናባሪ" ንግድ የሚያካሂዱትን ሕገወጦች፤ መቶ አለቃ ዊንጌት እያደነ ለመያዝ በወሰደው የጠነከረ እርምጃ፤ እጅግ የሚያስደንቅ ውጤት ለማስገኘት ቻለ። በዚህ በኢትዮጵያና በሱዳን ወሰን ላይ ሲካሄድ የቆየውን ሕገወጥ የንግድ ሥራ አድፍጦ በማጥመድ ዊንጌት የተጠቀመበትን ዘዴ፤ እሱም ወደ ሌላ ቦታ ከተዛወረ በኋላ ባለሥልጣኖቹ እንዲቀጥል በማድረጋቸው፤ የወጣቱ መኮንን ስምና መልካም ዝና ለብዙ ጊዜ ሲደነቅ የኖረ ሆኗል።

እ.ኤ.አ በ1936 ዓ.ም ኦርድ ዊንጌት በታላቋ ብሪታንያ ሞግዚትነት በሚተዳደረው በፓሊስቲን ተዛውሮ፤ በዚያ ላለው የጦር ሠራዊት የመረጃ መኰንን ሆነ። ወጣቱ የጦር መኰንን ፓሌስቲን ከደረሰበት ዕለት ጀምሮ፤ አይሁዳውያኖች ነፃነታቸውን ለማወጅና የእሥራኤልን መንግሥት ለማቋቋም የሚያደርጉትን ጥረት ከልቡ የሚደግፍና የሚያምንበት በመሆኑ፤ የዕብራይስጥን ቋንቋ ሌት ተቀን አጥንቶ በሁለት ዓመት ጊዜ ውስጥ፣ ቋንቋውንና ሥነ ጽሑፉን ማወቅ ቻለ። ዊንጌት፤ ምንም እንኳ የይሁዳ ዘር እንደሌለበት የታወቀ ቢሆንም፤ ለእነሱ ያለው ስሜትና ድጋፍ ከሚገባ በላይ ግልጽ ሆኖ በመታየቱ፤ በአለቆቹ ዘንድ የተወደደ አልነበረም። ወጣቱ መኰንን በሞያው ደፋርና መንፈሰ ጠንካራ፣ ብልህና አስተዋይ ከመሆኑም በላይ፤ በሚያምንበት ፀንቶ መገኘቱ መልካም ዝና ቢያተርፍለትም፤ በሌላ በኩል ደግሞ ለበላዮቹም ሆነ ለበታቾቹ፤ ተግባቢ ወይም ምቹ የሆነ ጠባይ ስለሌለው፤ አስቸጋሪና እምቢተኛ ነው የሚል አስተያየት ተወስዶበታል።

እ.ኤ.አ ከ1936 እስከ 1939 ዓ.ም ድረስ በፓለስቲን በኖረበት ዘመን፤ ከዚህ በፊት እንደተገለጸው ከይሁዲዎቹ ጋር የሚያደርገው መቀራረብና ወዳጅነት፤ ከዚህም አልፎ በሚችለው ሁሉ የአገሩ ነዋሪ ከሆኑት ዓረቦች ጋር ልዩነት እየፈጠረ፤ ለይሁዲዎቹ ፊት ለፊት የሚያደርገው አድልዎ የበላይ አለቆቹን እጅግ አድርጐ የሚያሳስባቸው ሆነ። ብዙ ምክርና ማስጠንቀቂያ ቢሰጠውም፤ ኦርድ ዊንጌት ከዕምነቱ አልዛነፍም አለ። እንዲያውም፤ ከቀን ወደ ቀን ለይሁዲዎቹ ያለው ጽኑ ድጋፍ እየጨመረ፤ ወጣቶቹን በሥውር የደፈጣ ውጊያ በማስተማር ለነፃነታቸው ለሚያደርጉት ጥረት ዋና ረዳታቸውና ፕላን ቀያሻቸው ሆነ።

እንግዲህ! ሚጀር ኦርድ ዊንጌት የተሰጠውን ሚሲዮን እየጣሰ፣ የፖለቲካውን ጉዳይ በመከታተል ይሁዲዎቹን ለመርዳት የሚሠራው ሁሉ አደገኛ ሆኖ ስለተገመተ፤ በግንቦት 1939 ዓ.ም በፓለስቲን የታላቋ ብሪታንያ ጦር አዛዥ የሆነው ዤኔራል ዌቨል፤ ከነበረበት ሥራ ላይ አስነሥቶ ወደ እንግሊዝ አገር እንዲመለስ አደረገው። በዚያን ጊዜ በፓሌስቲን የነበሩት የዊንጌት አለቆችም ስለ መኰንኑ የገለጹት አስተያየት " ... ኦርድ ዊንጌት በሞያው የሚከበር ጀግና ወታደር ቢሆንም፤ ከተሰጠው ተግባርና ኃላፊነት እየወጣ የሚያደርገው የፖለቲካ ንቅናቄ አደገኛነቱ በግልጽ ስለሚታይ፤ ከፓሌስቲን መዛወሩ ብቻ ሳይሆን ወደፊትም የፓሌስቲንን ጉዳይ በሚመለከት ሥራ መመደብ የለበትም ... " የሚል ስለሆነ፤ የፓሌስቲን የጦር አዛዥ ይህንኑ ሐሳብ ተቀብሎ ከመፈጸም በስተቀር ሌላ መንገድ አልነበረውም። ይሁን እንጂ፤ ዤኔራል ኧርል ዌቨል፤ ሜጀር ዊንጌት ከተሰጠው ኃላፊነት እየወጣ፤ ለይሁዲዎቹ ድጋፍ ሰጭ ሆኖ መገኘቱ የተገባ አለመሆኑን ደህና አድርጐ ቢያውቅም፤ ስለ መኰንኑ የውትድርና ሞያ ያለውን አድናቆት አልቀነሰም ነበር። ስለዚህም፤ "ሞዓ አንበሳ ዘእምነገደ ይሁዳ" ለተባለው ለኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ዘውድ፤ ኦርድ ዊንጌት መልካም አስተያየት እንደሚኖረው ስለሚያምን፤ በካርቱም ስብሰባ በተወሰነው መሠረት፤ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመቻ ዝግጅትና ኃላፊነት ከእሱ የተሻለ ሌላ የጦር መኰንን አይታየኝም ብሎ አቀረበው።

የጦር ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደንም፤ ስለ ዊንጌት የቀረበለትን የመረጃ ሪፖርት በዝርዝር ከተመለከተ በኋላ፤ የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር አዛዥ ዤኔራል ዌቨል በሰጠው ሐሳብ ተስማምቶ፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት በፋሽስት ላይ ለሚያደርጉት ዘመቻ አዘጋጅና የኦፐሬሽኑ መሪ እንዲሆን፤ በሌተና ኮሎኔልነት ማዕረግ ሹመቱን አጸደቀለት። ዊንጌት፤ ከፓሌስቲን ወደ እንግሊዝ አገር ከተዛወረበት አንድ ዓመት ተኩል ከሚሆን ጊዜ ጀምሮ፤ የበላይ አለቆቹ በእሱ ላይ

መልካም አስተያየት እንደሌላቸውና ለወደፊቱም የተሻለ ዕድል እንደማይሰጡት ተስምቶት ሞራሉ ተዳክሞ ነበር። በኅዳር ወር 1940 ዓ.ም መጀመሪያ ላይ በኢትዮጵያ ከፋሽስት ጋር ለሚደረገው ጦርነት፣ በሌተና ኮሎኔልነት ማዕረግ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የዘመቻ ጦር አዘጋጅና መሪ እንድትሆን ተመርጠሃል የሚለው ቴሌግራም ሲደርሰው፣ ያልጠበቀውና ያላሰበው በመሆኑ፣ ለጊዜው ማመን አቅቶት ነበር። ጄኔራል ዌቨል እንደገመተው፣ የኢትዮጵያ ነገሥታት ከይሁዳ የዘር ሐረግ አላቸው እየተባለ የሚነገረውን ታሪክ ዊንጌት በመልካም አስተያየት ስለሚመለከተው፣ ይህን የተሰጠውን ኃላፊነት የተቀበለው እጅግ በጋለ መንፈስ ነው። በዚህም መሠረት፣ የዚህን የዘውድ ታሪክና የኢትዮጵያን ሕዝብ ነፃነት ለማስመለስ፣ በቆራጥነትና በጀግንነት ተዋግቶ ጠላትን ድል እንደሚያደርግ ታጥቆ መነሣቱን ለጄኔራል ዌቨል ካስታወቀ በኋላ፣ ኦርድ ዊንጌት ጊዜ ሳይፈጅ ገሥግሶ ወደ ሱዳን መጣ።

ዊንጌት ካርቱም እንደደረሰ፣ ከሁሉ አስቀድሞ በሰፊው የተነጋገረው የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የፖለቲካ ኦፊሰር ሆኖ ከተመደበው ከቻፕማን አንድርውስ ጋር ነበር። ንጉሠ ነገሥቱ ከሎንዶን ተነስተው ካርቱም ከደረሱበት ካለፉት አምስት ወራት ጀምሮ፣ የሱዳን አገረ ገዢ ሰር ስቲዋርት ሳይምስና፣ የጦሩ አዛዥ ጄኔራል ዊሊያም ፕላት፣ የጃንሆይን መምጣት ባለመቀበል የፈጸሙባቸውን በደል ዘርዝሮ ስለአስረዳው፣ ዊንጌት እጅግ አድርጐ አዘነ።

ቻፕማን ለዊንጌት በሰፊው እንዳስረዳው፣ በሱዳን ያሉት ባለሥልጣኖች አገረገዢው ስቲዋርት ሳይምስና የጦር አዛዡ ዊሊያም ፕላት፣ ሙሶሊኒ ከሂትለር ጋር መሰለፉን ከማወጁ በፊት፣ ለፋሽስቱ መንግሥት አድናቂዎችና በተለይም የኢትዮጵያ ምክትል ንጉሥ (Vice Roy) ከሆነው ከዱካ-ዱ-አስታ ጋር ከፍ ያለ የወዳጅነት ግንኙነት ነበራቸው። ይህ ወዳጅነት የተመሰረተው፣ በሱዳንና በኢትዮጵያ ወሰን ላይ የሚንቀሳቀሱትን ሽፍቶችና ሕገ ወጥ የኮንትሮባንድ ነጋዴዎች ተባብረው ለማጥፋት የወሰዱትን እርምጃ ምክንያት በማድረግ ነው። ለዚህም፣ የኢትዮጵያ ም/ንጉሥ የተባለው ካርቱም መጥቶ ጉብኝት ሲያደርግ፣ ከፍ ያለ አቀባበልና መስተንግዶ ተደርጐለታል። በተጨማሪም የፋሽስቱን መንግሥት እነ ፕላት የሚፈሩት፣ በምሥራቅ አፍሪካ በኢትዮጵያና በኤርትራ፣ በሶማሌን፣ በሊቢያ ያሠፈረው የምድር ጦር ኃይል ከግማሽ ሚሊዮን በላይ ሲሆን፣ ያሉትም የአየር ኃይል ተዋጊ አይሮፕላኖች ቁጥራቸው ከአምስት መቶ በላይ እንደሆነ ይገመታል። በዚህ አንፃር፣ ታላቋ ብሪታኒያ ግን፣ በግብፅና በሱዳን፣ በፓሌስቲንና በኤደን፣ እንዲሁም በኬንያና በዑጋንዳ ያላት የጦር ኃይል ከመቶ ሺህ አይበልጥም። ስለዚህ፣ በካርቱም ያሉት ባለሥልጣኖቻችን ለፋሽስት መንግሥት ካላቸው መልካም የሆነ የግል ስሜት በላይ፣ የሙሶሊኒ የጦር ኃይል እጅግ አድርጐ የሚያሠጋቸው ስለሆነ፣ ለኢትዮጵያ ነፃነት የሚያስቡ ወይም የሚጨነቁ አይደሉም፣ ሲል ቻፕማን አንድርውስ፣ ትክክለኛውን ሁኔታ ደህና አድርጐ አብራርቶለታል።

ኦርድ ዊንጌት፣ ቻፕማን የገለጸለትን ጠቅላላ ሁኔታ ካዳመጠ በኋላ፣ በወጉ መሠረት ወደ ጄኔራል ፕላት ቢሮ ሄዶ ቪዚት አደረገ። ከዚያም በቀጥታ ከካርቱም ሠላሳ ማይልስ ርቆ ወደሚገኘው ወደ ጀበል አውልያ በአውቶሞቢል ተጉዞ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጋር ተገናኝቶ ተዋወቀ። በዚህ ጊዜ ንጉሠ ነገሥቱ የተቀበሉት በሞቀ መንፈስ ሲሆን፣ እሱም በደስታ መንፈስ የሚከተለውን ንግግር አደረገላቸው።

ጃንሆይ! እኔ ወደ እርስዎ የመጣሁት ትልቅ ኃላፊነት ተቀብዬ ነው። ከባድ ነው ብዬ የምጠራው ኃላፊነት፣ በፋሽስት መንግሥት በግፍ የተቀማውን የአገርዎን ነፃነት ለማስለቀቅና የግርማዊነትዎ የንጉሠ ነገሥትነት ዘውድ በመንበርዎ ላይ እንዲመለስ ለማድረግ ስለሆነ ነው። ይህም ሐሳብ በቅርብ ጊዜ ውስጥ ምናልባትም ቢበዛ በሚቀጥሉት ስድስት ወራት ውስጥ እንዲፈጸም የሚያስፈልግ ነው። የግርማዊነትዎ ዘመቻ የሚያመራው፣ ከሱዳን በቀጥታ እስከ መናገሻ ከተማዎ እስከ አዲስ አበባ ስለሆነ፣ የመጀመሪያው ግዳጃችን የጉጃም ግዛትዎን ነፃ ማድረግ ነው። ሌሎቹን የምንሠራቸውን ሁሉ በፕላን እየቀየስን በየመልካቸው እርምጃ እንወስድባቸዋለን።

እስከ ዛሬ ድረስ ግርማዊነትዎ የደረሰብዎትን መከራና ፈተና፣ በሰፊው ትዕግሥትዎና በማይበገረው ጥንካሬዎ እንደተቋቋሙት ሁሉ፣ አሁንም ከፊታችን የተደቀነውን ከባድና አስቸጋሪ የሆነውንም የነፃነት ትግል አሸንፈው፣ ለድሉ ደስታ እንደሚበቁ እርግጠኛ ነኝ። ለዚህም ግብ፣ የጦሩን ፕላን እንዳዘጋጅና የግርማዊነትዎን ዘመቻ እንድመራ፣ ከአገሬ ከታላቋ ብሪታኒያ መንግሥት ኃላፊነቱን እንድቀበል በመመረጤ የተሰማኝን ጥልቅ የሆነ ክብርና ደስታ ሳልገልጽልዎ ማለፍ አልፈልግም።

ጃንሆይ! እንግዲህ እስከዛሬ ሲያደርጉት እንደቆዩት ሁሉ፣ እምነትዎን እንዲያጸኑ ተስፋዎን እንዲያጠነክሩ እያሳሰብኩ፣ በመጨረሻም ድሉ የእርስዎ መሆኑን እንዲያውቁት ከልብ የመነጨ መልካም ሐሳቤንና መልካም ምኞቴን አቀርብልዎታለሁ።

ከዊንጌት ንግግር በኋላ፣ ጃንሆይም ወዲያውኑ አከታትለው አጠገባቸው በነበሩት በአርበኛው በአቶ መኩንን ደስታ አስተርጓሚነት የሚከተለውን መልስ ሰጡ።

" ... የታላቋ ብሪታንያ የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር ጠቅላይ አዛዥ ጄኔራል ዌቭል የእርስዎን መሾም ሲገልጹልኝ፣ አያይዘው የላኩልኝን የሕይወት ታሪክዎን አንብቤ እጅግ ደስ ብሎኛል። የጠለቀ ከፍተኛ ትምህርት የፈጸሙና በውትድርና ሞያዎም፣ እስከዛሬ ያከናወኑት ሁሉ የተወደደና የተደነቀ በመሆኑ፣ በኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትነቴ ሹመትዎን የተቀበልኩት፣ ከታላቅ ደስታና ከሙሉ ዕምነት ጋር ነው። የተሰጠዎትን ከፍተኛ ኃላፊነት ከግቡ ለማድረስ በሚያደርጉት ጥረት፣ ፈጣሪያችን እንዲረዳዎ ጸሎታችንና መልካም ምኞታችን አይለይዎትም። ... አሁን ስለ እኔ ሲናገሩ፣ " ... እስከአሁን የደረሰብዎትን መከራና ፈተና በትዕግሥት ለመቋቋም ያሳዩት ጥንካሬ የሚደነቅ ነው ... " ብለውኛል። ስለዚሁ መልካም አስተያየትዎ ከልቤ የሚሰማኝንና የማምንበትን እውነቱን ልገልጥልዎ እወዳለሁ። የኢትዮጵያን ሕዝብ እንድመራ ከባዱን ኃላፊነት የተቀበልኩት በእግዚአብሔር ፈቃድና በሕዝቤ ፍላጐት ስለሆነ፣ ያለብኝን ግዳጅ ለመፈጸም ማናቸውም መከራና ፈተና ሊገታኝ አይገባም። በሕይወት እለሁ ድረስ፣ በአገሬ ጉዳይ ማናቸውንም ችግር መቀበልና መቋቋም አለብኝ። ስለዚህም፣ እስከ ዛሬ የደረሰብኝን ሁሉ ከምንም አልቆጥረውም። ዋናው ዓላማዬ፣ የአገሬ ነፃነት ከባዕድ ቀንበር እስኪላቀቅ ድረስ፣ ከእኔ የሚጠበቀውን ሁሉ በተቻለኝ አሟልቶ መፈጸም ስለሆነ፣ ወደፊትም በማደርገው ጥረት ብዙ ፈተና እንደሚገጥመኝ ደህና አድርጌ አውቃለሁ። ስለዚህም፣ የወደፊቱን ሕይወቴን ተዝናንቼ አልመለከተውም።

ለክቶውም ሆነ ለደጉ ተዘጋጅቼ መገኘት አለብኝ። በዚህም መሠረት እርስዎ በተሰጠዎ ኃላፊነት በሚያደርጉት የዘመቻ ዝግጅት፤ በሚፈልጉበት ቦታና በሚያስፈልግዎ ዓይነት፤ ያለ አንዳች መታከት አብሬዎ እንደምቆም አረጋግጥልዎታለሁ። እንደሚያውቁት፤ ግፈኛው የፋሽስት መንግሥት በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ ከሰብዓዊ መንፈስ ውጭ የሚያደርሰው ሥቃይና መከራ፤ ወሰንና ወደር የሌለው መሆኑ በዓለም ታሪክ ላይ ተመስክሮበታል። ይህ ሕዝብ፤ የእኔን የንጉሠ ነገሥቱን ሱዳን መድረስና በታላቋ ብሪታንያ እርዳታ በጠላታችን ላይ ለመዝመት ዝግጅት ላይ መሆናችንን ሰምቶ፤ ለነፃነቱ መሥዋዕትነትን ለመቀበል ቆርጦ ይጠብቀናል። ስለዚህ፤ ይህ የቆረጠ ዕምነትና ይህ የነቃ መንፈስ በጊዜ ብዛት ተሰላችቶ እንዳይወድቅብን፤ ሥራችንን ማፍጠን ያለብን መሆኑን ሳላስብዎ እወዳለሁ ... " ካሉ በኋላ፤ ጃንሆይ በንግግራቸው መጨረሻ ላይ እግዚአብሔር ሥራዎንና ድካምዎን ይባርክልዎ የሚለውን ምርቃት ሰጥተዋል። እንግዲህ! ከዚህ በላይ እንደታየው፤ ዊንጌት ያደረገው የመተዋወቂያ ንግግር ንጉሠ ነገሥቱን ምን ያህል እንዳስደሰታቸውና፤ ጃንሆይም የሰጡት መልስ ዊንጌትን የቱን ያህል ስሜቱን እንደነካው መገንዘብ ይቻላል። መቸም መልካም በሆነ የመግባባት መንፈስ የሚጀመር ሥራ ውጤቱ እንደሚያምር አያጠራጥርም።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሱዳን ከመጡበት ጊዜ ጀምሮ፤ ባለፉት አምስት ወራት ውስጥ፤ በቁጥር 101 የተመደበው የኮሎኔል ሳንድፎርድ፣ የአዛዥ ከበደ እና የጌታሁን ተሰማ ሚሲዮን፤ በኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ ገብቶ ከሚያካሂደው መልካም ተግባር በስተቀር፤ ሌላ የተሠራ አንዳች ነገር አልነበረም። ስለዚህ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመቻ ዝግጅቱ የሚጀመረው፤ ዊንጌት ከተሾመ በኋላ መሆኑ ለማንም ግልጽ ነው። እነ ዊሊያም ፕላት፤ ከፋሽስት ጋር ለሚደረገው ጦርነት የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ለአንዱ ግንባር እንኳ የዘመቻ መሪነት ቦታ ሊሰጣቸው አይገባም በማለት፣ በሱዳን አካባቢ የሚገኙትን የኢትዮጵያን ተዋጊ አርበኞች አሰባስቦ ሥልጠና ለመስጠትም ሆነ ለማዘጋጀት አሻፈረን ብለው የአምስት ወራት ጊዜ በከንቱ አቃጠሉ። የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር አዛዥ ጄኔራል ዌቭል እና የጦር ሚኒስትሩ አንቶኒ ኢደን የፕላትን የተቃውሞ አቋም ስለተረዱት፤ እርድ ዊንጌት ለሚያደርገው ዝግጅት እሱ ራሱ በቀጥታ የሚያዝበት አንድ ሚሊዮን ፓውንድ የሥራ ማስኬጃ በጀት መደቡለት። ለዊንጌት ይህ የተሰጠው በጀት ከጦር መሣሪያዎች በስተቀር ተዋጊዎቹን ለማሠልጠኛና ለስንቅ ማደራጃ እንዲሁም ለትራንስፖርት የሚያስፈልጉትን ወጭዎች ሁሉ ስለሚሸፍንለት፤ ዊሊያም ፕላትን ከመለማመጥ አድኖታል።

ዊንጌት ከተሾመ በኋላ፤ ጄኔራል ፕላት ተስፋ አድርጉ የተጠባበቀው፤ ሰውየው በጠባዩ አስቸጋሪነት የታወቀና እኔ ያልኩት ብቻ ካልተፈጸመ የሚል ስለሆነ፤ ከንጉሠ ነገሥቱ ጋር መጋጨቱ ስለማይቀር፤ በዊንጌት የሚተካውን መኰንን እኔ መርጨ የፈለግኩትን ማድረግ እችላለሁ ብሎ አልሞ ነበር። ነገር ግን ይህ ምኞት ሊሳካለት አልቻለም። ቀደም ሲል እንደተገለጸው፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና ዊንጌት በጀበል አውልያ ተገናኝተው እንደተዋወቁ በመካከላቸው ከፍ ያለ የመግባባትና የመቀራረብ መንፈስ ስለተፈጠረ፤ የፕላት ምኞት ከንቱ ሆኖ ቀርቷል። በዚህም አኳኋን፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመቻ የሚዘጋጀውና የሚራመደው፤ በእርድ ዊንጌት ፕላን እንጂ በዊሊያም ፕላት ጠማማ አስተሳሰብ ሊሆን አልቻለም።

# ምዕራፍ ፲

## የነፃነት ጉዞ ወደ ኢትዮጵያ፤ ከካርቱም እስከ አዲስ አበባ

የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመቻ አዘጋጅና የውጊያው መሪ እንዲሆን በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የተሾመው ሜጀር እርድ ዊንጌት፤ በምድረ ሱዳን በሁለት ወራት ጊዜ ውስጥ አንድ ሺህ ሰባት መቶ የሚሆኑ ተዋጊ ወታደሮችን አሠልጥኖ አዘጋጃቸው። እነዚህ ተዋጊዎች ግማሾቹ ኢትዮጵያውያን ሲሆኑ፤ ግማሾቹ ደግሞ የሱዳን ዜጎች ነበሩ። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሱዳን ከመጡበት ጊዜ ጀምሮ ደጋግመው እንደአሳሰቡት፤ የሱዳን አገረ ገዥ የሰር ስቲዋርት ሳይምስንና የእንግሊዝ ጦር አዛዥ የጄኔራል ዊሊያም ፕላትን ትብብር በማግኘት፤ በኬንያ፣ በጂቡቲና በሱማሊያ ተዘጋጅተው የሚጠባበቁትን ኢትዮጵያውያን አርበኞችንና ስደተኞችን በሙሉ ወደ ሱዳን ለማስገባት ቢቻል ኖሮ፤ ዊንጌት የሚያዘጋጀው ጦር ቁጥሩ በጣም ከፍ ያለ በሆነ ነበር። ባለፈው ምዕራፍ እንደተገለጸው፤ ስለዚሁ ጉዳይ ጃንሆይ ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና ለጦር ሚኒስትሩ አንቶኒ ኢደን ባመለከቱ ጊዜ፤ በምሥራቅ አፍሪካ የሚገኙት የኢትዮጵያ አርበኞችና እንዲሁም በአገር ፍቅር ስሜት ተቀስቅሰው ወደ ዘማቾች የሆኑት ኤርትራውያኖች፤ ወደ ሱዳን እንዲገቡ የተፈቀደ መሆኑ ተነግሮአቸው ነበር። ነገር ግን፤ በምሥራቅ አፍሪካ ያሉት የእንግሊዝ የጦር ባለሥልጣኖች፤ ከጥቂቶች አርበኞች በስተቀር ብዙዎቹን በተለይም ወደ ዘማቾች የሆኑትን ኤርትራውያኖች ልዩ ልዩ ምክንያት እየፈጠሩ ወደ ሱዳን እንዳይሻገሩ መንገዱን ዘጉባቸው። እንደሚታወቀው፤ በምሥራቅ አፍሪካ የሚገኙት የእነዚህ የእንግሊዝ የጦር ባለሥልጣኖች ዋና ዓላማ፤ ፋሽስትን ከኢትዮጵያ ግዛት ለማስለቀቅ ጄኔራል ካኒንግሐም በደቡብ በኩል፤ ጄኔራል ፕላት በሰሜን፣ ለሚያደርጉት ውጊያ የተሟላ የጦር መሣሪያና የተሟላ የሰው ኃይል እንዲኖራቸው ማድረግ እንጂ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በምሥራቅ ግንባር ለሚመሩት ዘመቻ የሚያስፈልጋቸውን ሁሉ ለመስጠት ፈቃደኞች አልነበሩም።

በምሥራቅ አፍሪካ ያሉት የእንግሊዝ የጦር ባለሥልጣኖች ስለ ኢትዮጵያ የወደፊት ዕድል የሚያስቡት ሁሉ፤ በኮሎኒያሊዝም መንፈስ ላይ የተመሠረተ መሆኑንና ከእነሱም ጋር መነታረኩ ምንም ውጤት እንደማይሰጥ እርድ ዊንጌት በትክክል ስለተረዳው፤ ባለው የሰው ኃይልና ባለው መሣሪያ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ዘመቻ ለመምራት ቆርጦ ተነሣ። በሱዳን ለመሰብሰብ የቻሉትን ቁጥራቸው አንድ ሺህ ሰባት መቶ የሚደርሱትን ተዋጊዎች በቀላል ዘዴ በማሠልጠንና በተገኙትም መሣሪያዎች አጠቃቀሙን እያንዳንዱ ወታደር በሚገባ እንዲያውቅ በማድረግ፤ ዊንጌት ዝግጅቱን ከአጠናቀቀ በኋላ፤ ዘመቻውን **"የጌዴዎን ኃይል"** ብሎ ሠየመው።

ይህ ቁጥሩ ሁለት ሺህ ለመድረስ ያልቻለው፤ "የጌዴዎን ጦር" ከሱዳን ወደ ጐጃም ለማምራት ሲነሣ፤ ከፊቱ የሚገጥመው የፋሽስት ጦር ኃይል ከዘመናዊ መሣሪያዎች ጋር ከሀያ ሺህ (20.000) በላይ የሚሆኑ ተዋጊ ወታደሮች ያሉት መሆኑ ታውቆ ነበር። ነገር ግን፤ በኮሎኔል ሳንድ ፎርድ፣ በአዛዥ ከበደ እና

በጌታሁን ተሰማ የሚመራው በቁጥር "101" የተመደበው ሚሲዮን፤ ቀደም ብሎ ወደ ኢትዮጵያ በመግባት በተለይም በጐጃም ውስጥ በልዩ ልዩ ቦታዎች ሲዋጉ ከኖሩት ታዋቂ አርበኞች ጋር በግልጽና በሰፊው በመነጋገር፤

- በመካከላቸው ለተፈጠረው አለመግባባት መፍትሔ በመስጠትና በማስታረቅ፣
- ከካርቱም ይዘዋቸው የመጡትን ልዩ ልዩ መሣሪያዎች በማደል፣
- ንጉሠ ነገሥቱ ከእንግሊዝ መንግሥት ባገኙት እርዳታ ጦራቸውን አሰልፈው ወደ ጐጃም ግዛት ለመግባት መቃረባቸውን በማስረዳት፣
- በጠቅላላው በያለበት የተሰማሩትን አርበኞች ሞራል በማዳበርና ጠላትን ከአገር ለማስወጣት ተዘጋጅተው እንዲጠባበቁ በማድረግ የተፈጸሙት ሥራዎች፣ አርድ ዊንጌት ለሚመራው የጌዴዎን ጦር በመላ ጐጃም ከፍ ያለ ደጀንና ኃይል አስገኘለት።

ንጉሠ ነገሥቱ ከካርቱም ወደ ኢትዮጵያ የዘመቻ ጉዞአቸውን ከመጀመራቸው ከሁለት ቀናት በፊት፤ ሁለት መቶ ለሚሆኑ ለእንግሊዝና ለሱዳን ታላላቅ ሰዎች፤ እንዲሁም አብረዋቸው ለከረሙትና ለሚከተሏቸው ኢትዮጵያውያን፤ በዚያው በጀበል አውልያ ማረፊያቸው ለመሰነባበቻ የሬሴፕሽን ግብዣ አደረጉ። እንደዚሁም በጉዞው ዋዜማ ምሽት፤ ዕብሪተኛ በመሆን ሲያስቸግር የቆየው በሱዳን የታላቋ ብሪታንያ ጦር አዛዥ ዤኔራል ዊሊያም ፕላት፤ ቀድሞ ከነበረው የተለወጠ መንፈስ በማሳየት፤ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መሰናበቻ ክብር በካርቱም ከፍ ያለ የራት ግብዣ ሰጥቶ ነበር። በዚህ ግብዣ ላይ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ሁለቱን ልጆቻቸውን ልዑል አልጋወራሽ አስፋወሰንንና ልዑል መኰንን የሐረር መስፍንን ወደ ዘመቻው ይዘዋቸው ለመሄድ መወሰናቸውን ለጋባዣቸው ገለጹለት። ይህንን ሐሳብ ፕላት አልደገፍም አለ። ምክንያቱንም ሲያስረዳ፤ በታሪክ የአንድ አገር ንጉሣውያን ቤተሰብ፤በጦር ዘመቻ ላይ በአንድነት ሲካፈል ታይቶ አይታወቅም። ምንም እንኳ ግርማዊነትዎ የሚመራው ጦር ድል ለማድረግ የተዘጋጀና የአገርዎን ነፃነት እንደሚያስመልስ ፅኑ ዕምነት የተጣለበት ቢሆንም፤ በዘመቻው ላይ አደጋ ሊከሠት እንደሚችል መርሳት የለብንም። ስለዚህ፤ ሁለቱ ልዑላን ልጆችዎ ከዘመቻው ቀርተው፤ ካርቱም በሚገኘው የጦር ትምህርት ቤት ውስጥ አንዳንድ የውትድርና ሞያ እያጠኑ ቢቆዩ ይሻላል ሲል አስተያየቱን ሰጠ። ጃንሆይ ሁለቱ ልጆቻቸው ከዘመቻው እንዲቀሩ የፕላትን ሐሳብ ለመቀበል አልፈለጉም ነበር። በዚያን ሰዓት አጠገባቸው የነበሩት ራስ ካሣ፤ ይኸ ሰው የሚናገረው ፍሬ ነገር ያለበት ሆኖ ታይቶኛል። የጃንሆይ ዘመቻ ዓላማው ድል አድርጐ ጠላትን ከአገር ማባረር ቢሆንም፤ በዚህ መሐል ድል መሆንና መሞትም እንደሚያጋጥም መታሰብ አለበት ሲል የተናገረው፤ ትክክለኛ አስተያየት ነው። በዚህ አኳኋን እነዚህን ልጆች ከእኛ ጋር የመጣውን ይካፈሉ ብለን ከአደጋው ውስጥ ማስገባቱ ጥቅም የለውም። እንግሊዞቹ እኛ በደህና እንጠብቃቸዋለን ብለው ቃል ሲሰጡ፤ አደራው የናንተው ነው ብለን ትተናቸው ብንሄድ ይሻላል ሲሉ የሰጡትን ሐሳብ ጃንሆይ አዳምጠው፤ በዚሁ እንዲፈጸም ተደረገ።

ዘመቻውን ለመጀመር በታቀደው ፕሮግራም መሠረት፤ እ.ኢ.አቆ ጥር 12 ቀን 1933 ዓ.ም የቃና ዘገሊላ በዓል ዕለት፤ (እ.ኤ.አ ጥር 20 ቀን 1941 ዓ.ም) ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከዋና ዋና ተከታዮቻቸው ጋር በልዩ አውሮፕላን "ሮዛይሪ" ከተባለው ግዛት ተነሥተው፤ በሱዳን ወሰን ላይ በሚገኘው "አሜድላ" በተባለው የኢትዮጵያ መሬት በማረፍ፤ "አረንጓዴ፣ ቢጫ፣ ቀይ" የሆነውን ባንዲራችንን



ንጉሠ ነገሥቱ ከሱዳን ተነስተው ዘመቻውን ወደ ኢትዮጵያ ሲጀምሩ፤ ከጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና ከጦር መሪዎቹ የተላኩላቸውን የመልካም ምኞት መግለጫዎች ሲቀበሉ፤

ተክለው የመጀመሪያውን የነፃነት የድል በር ከፈቱ። በዚች ታሪካዊ በሆነች ቀንና ሰዓት፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ባደረጉት ንግግር ልባዊ ስሜታቸውን የገለጹት፤ " ... ከመማረክ መሞት፤ ለጠላት ከመገዛት መሰደድ፤ ይበጃል። በሃይማኖቱና በዕምነቱ የፀና በእግዚአብሔር እርዳታ ተስፋው ሲፈጸምለት የማየት ዕድል ይገጥመዋል። ይኸው! እኔም በውቅያኖስ ባሕርና በምድረበዳ ተሻግሬ፤ መጣሁልሽ አገሬ ብዬ የአገሬን መሬት ለመርገጥ በቅቻለሁ ... " በሚል ቃል ነበር።

ንጉሠ ነገሥቱ በዚህ "ኦሜድላ" በተባለው ቦታ ላይ ሰንደቅ ዓላማችንን አውለብልበው የኢትዮጵያ ሕዝብ መዝሙር ከተዘመረ በኋላ፤ በእንግሊዞች በኩል ለጃንሆይ አማካሪ እንዲሆን የተመደበው "ቻፕማን አንድርውስ" ከጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና ከጄኔራል ዊሊያም ፕላት የተላከላቸውን መልዕክት አቀረበላቸው። ቸርችል በገለጸው አስተያየት፤ " ... ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለብዙ ወራት ያሳዩት ትዕግሥትና ቆራጥነት በመጨረሻው ፍሬውን ሰጥቶ፤ ዘመቻውን ለማዘጋጀትና ዓላማውን ለመጀመር ስለአስቻለ፤ የጋለ ደስታዬንና መልካም ምኞቴን መግለጥ እወዳለሁ ... " ካለ በኋላ፤ " ... ንጉሠ ነገሥቱ ወደፊት አገራቸው ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር ስለሚኖራት ግንኙነት ጉዳይ አንድ ዓይነት የቃል ኪዳን ስምምነት እንዲደረግ የጠየቁት፤ ጠላት ድል ሆኖ እሳቸው ከመናገሻ ከተማቸው ከገቡ በኋላ የሚፈጸም ስለሆነ፤ አሁን ጊዜውም ሁኔታውም የሚያመች አይደለም ... " ብሏል።

እዚህ ላይ መገንዘብ እንደሚቻለው፤ ጃንሆይ ሱዳን ከደረሱበት ጊዜ አንሥቶ የዘመቻው ዝግጅት እንዲፋጠንላቸው ለቸርችል በላኳቸው በብዙዎቹ ቴሌግራሞቻቸው ውስጥ፤ ኢትዮጵያ ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር ወደፊት ስለሚኖራት ግንኙነት ከአሁኑ የቃል ኪዳን ስምምነት እንዲደረግ ደጋግመው ሲያሳስቡ ቆይተዋል። ቸርችልና ኤደን ግን ይህንን ጉዳይ ለማከናወን አሁን ጊዜው አይደለም የሚለውን አስተያየታቸውን መለወጥ አልፈለጉም። ጃንሆይ ከእንግሊዞች ጋር በተቻለ ፍጥነት የቃል ኪዳን ውል <u>መፈራረም ያስፈልጋል</u> ብለው እስከዚህ ድረስ ያሳሰባቸው ምክንያቱ ምን እንደሆነ ገልጠው ባይናገሩትም፤ ጠላት ድል ሆኖ ኢትዮጵያን ለቅቆ ከወጣ በኋላ፤ እነዚህ ቅን መንፈስ የሌላቸው የታላቋ ብሪታንያ የጦር መሪዎች እነ ጄኔራል ፕላት፤ አገራችንን በመያዝ የኮሎኒ አስተዳደር ዘርግተው እንዳያስቸግሯቸው በመሥጋት መሆኑ ለማንም የተሠወረ አይሆንም። ያም ሆነ ይህ በሁለቱ አገሮች፤ በኢትዮጵያና በታላቋ ብሪታንያ መካከል እንዲፈረም የተጠየቀው ውል፤ አስፈላጊ መሆኑ ታምኖበት የተከናወነው፤ እነ ቸርችል እንዳሉት ከነፃነት መመለስ በኋላ እንጂ፤ ንጉሠ ነገሥቱ እንደፈለጉት በዘመቻው ወቅት መሆን አልቻለም። የዚህም ውል ዝግጅትና አፈጻጸም በምን መልክ እንደቀረበና እንደተከናወነ ታሪኩን እየተከተልን ስንጓዝ ወደፊት እናገኘዋለን።

ቀደም ሲል እንደተነገረው፤ "ኦሜድላ" በተባለው በሱዳን ወሰን በሚገኘው የጉጃም ግዛት ላይ የመጀመሪያውን ድል አብሣሪ የሆነውን የኢትዮጵያን ሰንደቅ ዓላማ ንጉሠ ነገሥቱ ከሰቀሉ በኋላ፤ የሚቀጥለው ፕሮግራም ለዘመቻው መምሪያ እንዲሆን ወደተመረጠው <u>"በላይ"</u> ወደተባለው አውራጃ መጓዝ ነበር። <u>ከኦሜድላ እስከ በላያ ድረስ ያለው ርቀት አንድ መቶ ሠላሳ ሁለት ኪሎ ሜትር የሚገመት ሲሆን፤</u> ጃንሆይ ከነአጀባቸው ከቦታው ለመድረስ ከሁለት ሳምንት የበለጠ ጊዜ ወስዶባቸዋል። ሕይወቱና የኢትዮጵያ እርምጃ በተሰኘው የታሪክ ማስታወሻቸው



በጐጃም ግዛት በሱዳን ወሰን ላይ ኦሜድላ በተባለው ቦታ፤ ንጉሠ ነገሥቱ የኢትዮጵያን ሰንደቅ ዓላማ በመስቀል የመጀመሪያውን የነፃነት የድል በር ከፈቱ። በግራ በኩል ደግሞ የሚታየው ጃንሆይ ሜጀር ዊንጌትን ሲያነጋግሩ ነው፤

ላይ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከኦሜድላ እስከ በላያ ስለአደረጉት ጉዞ የገለጹት የሚከተለውን ነው። " ... ከኦሜድላ ተነሥተን ወደ በላያ ስንሄድ፣ መንገዱ ጉራንጉርና ጥቅጥቅ ያለ ቁጥቋጦ የበዛበት ስለሆነ፣ በቀን ከሰባት ኪሎ ሜትር የበለጠ መጓዝ አልተቻለም ነበር። ከዚህ በላይ ደግሞ፣ የአየሩ በረሃማነትና የፀሐዩ ሐሩር እጅግ የሚያሰቃይ ስለሆነ፣ እንኳንስ ሰዎች እንስሶችም የሚቋቋሙት አይደለም። የምንጓዘውም ከወታደሮቻችን ጋር በትልልቅ ካሚዮኖች ተጭነን ስለሆነ፣ ከመንገዱ አስቸጋሪነት የተነሣ የተሽከርካሪው የጉዞ ፍጥነት አንድ ግመል ከሚያደርገው እርምጃ የሚበልጥ አልነበረም። አንዳንድ ጊዜ ደግሞ ከፀሐዩ ቃጠሎና ከሙቀቱ ኃይል የተነሣ፣ ቀኑ መሽቶ በምናርፍበት ቦታ የመጠጥ ውሃ እስከማጣት የደረስንበት ቀን ነበር። ... ከዚህ በላይ በተገለጸው አኳኋን፣ ለአሥራ ሰባት ቀናት በሥቃይ ስንጓዝ ከከረምን በኋላ፣ ጥር 29 ቀን 1933 ዓ.ም "በላያ" ስንደርስ፣ ባላሰብነውና ባልጠበቅነው መንገድ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ አርበኞቻችን ተሰልፈው፣ በፉከራና በቀረርቶ መንፈስን በሚያስደስትና በሚያኮራ ሁኔታ ሲቀበሉን፣ ከደስታችን ብዛት የተነሳ ያንን ሁሉ ያሳለፍነውን የሥቃይ ጉዞ በአንድ ጊዜ ረሳነው ... " ብለዋል።

"በላያ" በጐጃም ግዛት ውስጥ ረባዳና ቆላ በሆነ አካባቢ የሚገኝ ስለሆነ፣ ከቦታው አቀማመጥና አለመመቸት የተነሣ፣ የፋሽስት እግር ሳይረግጠው የቆየ ነው ይባላል። የንጉሠ ነገሥቱ ዘመቻ ጊዜያዊ ጠቅላይ መምሪያ በዚሁ በ "በላያ" እንዲሆን የተወሰነውም፣ የጠላት ኃይል በአውሮፕላን ቦንብ በመጣል ካላጠቃ በስተቀር፣ በምድር ጦር ደፍሮ መሞከር አይችለውም ተብሎ ስለታመነበት ነው።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በላያ ከመድረሳቸው በፊት ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ አዛዥ ከበደ እና አቶ ጌታሁን ተሰማ፣ ከኮሎኔል ሳንድፎርድ ጋር ሆነው "ሚሲዮን 101" የተባለውን የመልዕክትና የጥናት ተግባራቸውን በመቀጠል፣ በመላ ጐጃም ላሉት አርበኞች የንጉሠ ነገሥቱን በላያ መድረስ እያስታወቁ፣ ያላቸውን ኃይል ከጌዴዎን ጦር ጋር እንዲያስተባብሩ ያደረጉት ከፍተኛ ጥረት ጥሩ ውጤት በማስገኘቱ፣ ለጃንሆይና ለአዝማቻቸው ለዊንጌት ከፍ ያለ እርካታ የሚሰጥ ሆኗል። በዚህም መሠረት ዊንጌት በነደፈው ፕላን፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከበላያ ተነሥተው ወደ ማህል አውራጃ ወደ ቡሬ እንዲያመሩና ከዚያም በተቻለ ፍጥነት ከጐጃም ዋና ከተማ ደብረማርቆስ ገብተው አረንጓዴ፣ ቢጫ፣ ቀይ የሆነውን ሰንደቅ ዓላማ በመትከል፣ የኢትዮጵያን ነፃነት እንዲያበሥሩ ነበር። ነገር ግን፣ በካይሮና በካርቱም ያሉት የታላቋ ብሪታንያ የጦር መሪዎች፣ የጌዴዎን አዝማች የጠየቃቸውን የአየር ኃይል ተዋጊ አውሮፕላኖች ድጋፍ ሳይሰጡ በመቅረታቸው፣ የታቀደውን ፕላን እንደታሰበው በፍጥነት ለመፈጸም ሳይቻል ቀረ። ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ በሱዳንና በካይሮ ያሉት የእንግሊዝ የጦር መሪዎች ዋናው ፍላጐታቸው፣ በደቡብ ኢትዮጵያ በኬንያ በኩል የተሠማራው የጀኔራል ካኒንግሐም ጦርና፣ በኤርትራ ላይ የዘመተው የጀኔራል ዊሊያም ፕላት ጦር ድሉን እንዲቀዳጁ ስለሆነ፣ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴና ለጌዴዎን ጦር ቅድሚያ መስጠት አስፈላጊ ነው ብለው አላመኑበትም። በዚህም አኳኋን ለጌዴዎን ጦር የተጠየቁትን የአየር ኃይል ድጋፍ ባለመስጠታቸው፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከበላያ ተነሥተው አንድ መቶ ሃምሳ ኪሎ ሜትር ያህል ርቆ ወደሚገኘው ቡሬ ወደተባለው ማህል ጐጃም ለመድረስ የሦስት ሳምንታት ጊዜ ወስዶባቸዋል። "ቡሬ" ላይ የባንዶች መሪ በመሆን መሽጐ በኢትዮጵያ የነፃነት ተዋጊዎች ላይ አደጋ እየጣለ ሲያጠቃ የቆየው የራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት ልጅ ማሞ ኃይለሚካኤል፣ በታወቁት አርበኞች በእነ ፊታውራሪ በቀለ አምባዬ፣ በእነ መኰንን ደስታና ጌታሁን ተሰማ ብርቱ ተጋድሎ፣ በየካቲት

ሐያ ቀን 1933 ዓ.ም ድል ሲሆን፣ "ቡሬ" በጌዴዎን ጦር ተያዘች። ከዚህ ቀን ጀምሮ ለጥቂት ጊዜ ንጉሠ ነገሥቱ ቡሬን ከበላያ ቀጥሎ ሁለተኛዋ የጦር ሠፈራቸው እንድትሆን አደረጓት።

ቡሬ፣ በጂዎግራፊ አቀማመጧ ከካርቱም ጋር ቀጥታ የአየርና የየብስ ግንኙነት ለማድረግ የምታስችል አማካይ ቦታ ስለሆነች፣ የጌዴዎን ጦር ጠላትን እያጠቃ ወደ ደብረማርቆስ ለመገስገስ ለሚያደርገው ዝግጅት ምቹ ሆናለች። እንደተጠበቀውም ባይሆን፣ በመጠኑ ከባድና ቀላል የሆኑ ዘመናዊ መሣሪያዎችን ከካርቱም ለማግኘት ስለተቻለ፣ ምንም እንኳ በጐጃም ዋና ከተማ ከያለበት ተሰብስቦ የተጠራቀመው የጠላት ሠራዊት ቁጥሩ ከአሥራ አምስት ሺህ (15.000) በላይ ይሆናል ተብሎ ቢገመትም፣ የጌዴዎን ጦር የተሰለፈው ሞራሉን ከፍ በማድረግ ነበር። ኦርድ ዊንጌት ካርቱም ላይ ላሉት ለበላዮቹ የእንግሊዝ ጦር አዛዦች አጠንክሮ ያመለከተው፣ አሁን በደብረማርቆስ የሰፈረው ቁጥሩ ከ15 ሺህ በላይ ይሆናል የተባለው የፋሽስት ጦር፣ ከቡሬ የምናደርገውን ንቅናቄ ሲሰማ በሽሽት አባይን ተሻግሮ ወደ ሸዋ እንዳያመልጥ በቂ የሆኑ የአየር ኃይል ተዋጊዎች ተሰጥተውት ጦሩን በአለበት ቦታ ሳይነቃነቅ ለመምታት እንዲቻል ነበር። ነገር ግን፣ በካርቱም ያሉት አዛዦች የዊንጌትን ሐሳብ አልተቀበሉትም። የአዛዦቹ ዋና ፍላጐት በደቡብ ኢትዮጵያ በኬንያና በሱማሌ በኩል ተሰማርቶ ወደ አዲስ አበባ የሚገሰግሰው የካኒንግሃም ጦር የበረታ የጠላት ኃይል ስላልገጠመው፣ እሱ ቀድሞ የንጉሠ ነገሥቱን መናገሻ ከተማ እንዲይዝ ዕድሉን ለማመቻቸት ነው። የጌዴዎን ጦር መሪ በዚህ በአዛዦቹ አስተያየት ቢያዝንም፣ ሞራሉ አልተጻከመም። በያለበት ያሉት የታወቁት የኢትዮጵያ አርበኞች፣ ንጉሠ ነገሥታቸው በአገራቸው መሬት በመካከላቸው ተገኝተው የውጊያው መሪና ተካፋይ ስለሆኑላቸው፣ ያላቸውን አቅም በማስተባበርና ቆራጥነታቸውን በማጠንከር ስለተዘጋጁ፣ የጌዴዎን አዛዥ ሙሉ ተስፋና ዕምነት አደረበት። በዚህም መሠረት በእነዚህ በታወቁት አርበኞች፣ በደጃዝማች ነጋሽ በዛብህና በደጃዝማች መንገሻ ጀምበሬ፣ በፊታውራሪ ኃይለየሱስ ፍላቴና በፊታውራሪ ገበየሁ ወልደማርያም የሚመራው የአርበኞች ጦር፣ በሚያስደስት ንቃት የተዘጋጀ በመሆኑ፣ ከቡሬ ወደ ደብረማርቆስ የተጓዘው የጌዴዎን ሠራዊት ጠላትን እያባረረ አንዳች እክል ሳይገጥመው ከግቡ ደረሰ።

ዊንጌት ትልቅ ሥጋት አድሮበት የነበረው፣ የጌዴዎን ጦር ከቡሬ ተነሥቶ ወደ ደብረማርቆስ ጉዞ መጀመሩ ሲታወቅ፣ በዚያ የተከማቸው በኮሎኔል ማራቪንታና የሚመራው ቁጥሩ እጅግ ብዙ የሆነው የፋሽስት ሠራዊት ተሸብሮ፣ የአባይን ወንዝ በመሻገር ወደ ሸዋ እንዳይሸሽ ነበር። ለዚህም፣ የጌዴዎን ጦር በጐጃም ውስጥ ከታወቀው ተዋጊና አርበኛ ከልጅ በላይ ዘለቀ ጋር በመተባበር፣ ደብረማርቆስ ላይ የሠፈረውን የማራቪንታኖን ሠራዊት ከበው ከካርቱም በሚደርሳቸው የአየር ኃይል በንብ ጣዮች እየተረዱ፣ የፋሽስት ጦር ሳይነቃነቅ አለበት ቦታ ለመጨፍለቅ ይቻላል የሚል ፕላን ነደፈ። ይህንንም ሐሳብ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሲነግራቸው፣ " ... ሐሳቡ መልካም ነው፤ ፈጻሚው እግዚአብሔር ነው ... " የሚል ቃል መለሱለት።

ዊንጌት በዘረጋው ዕቅድ መሠረት፣ ከረዳቶቹ ከእንግሊዞች የጦር መኰንኖች መካከል፣ ከምኒልክ ዘመን ጀምሮ ለአሥር ዓመታት በኢትዮጵያ የታላቋ ብሪታንያ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ከነበረው ከዊልፍሪድ ቴሲገር (Wilfred Thesiger) አዲስ አበባ የተወለደውንና ስለ ኢትዮጵያም ልዩ ፍቅርና አስተያየት ያለውን መኰንን መርጦ ከልጅ በላይ ዘለቀ ጋር እንዲደራደር ላከው። የዊንጌት ዋና ዓላማ፣

ደብረማርቆስ ላይ የሠፈረው በኮሎኔል ማራቪንታና የሚመራው የፋሽስት ሠራዊት የጌዴዎን ጦር መንቀሳቀሱን ሲሰማ፤ የአባይን ወንዝ ተሻግሮ እንዳያመልጥ ከልጅ በላይ ዘለቀ ሠራዊት ጋር ለመከበብና ለማጥቃት መሆኑን በመግለጽ፤ ቴሲገር የተላከበትን መልዕክት በዝርዝር አስረዳ።

ልጅ በላይ ዘለቀ፤ እንግሊዛዊውን መኰንን ቴሲገርን ተቀብሎ፤ በደህና እያስተናገደው ጥቂት ቀናት ካሳለፈ በኋላ፤ ዊንጌት ላሰበበትና ላቀረበው ሐሳብ እንዳች እርምጃ ሳይወስድ፤ የፋሽስት ጦር ደብረማርቆስን ለቅቆ አባይን በመሻገር ወደ ፍቼ ማምለጡ ተሰማ። አርድ ዊንጌትና ቴሲገር በየማስታወሻቸው እንደጻፉት፤ ያ ሁሉ የፋሽስት ጦር (ከ12-15 ሺህ የሚደርስ) አባይን ለመሻገርና ለማምለጥ የቻለው፤ በበላይ ዘለቀ እርዳታ ነው በማለት ምሬታቸውን ገልጸዋል። ልጅ በላይ ዘለቀ ይህንንም አሳዛኝ ድርጊት የፈጸሙት፤ የጠላት ወገን የሆኑት ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት " ... የፋሽስት ወታደሮች ከደብረማርቆስ ወጥተው ምንም ሳይነካቸው በደህና አባይን እንዲሻገሩ ካደረግክልኝ፤ ልጄን እድርልሃለሁ። በዚህም አኳኋን ከንጉሥ ተክለሃይማኖት ቤተሰብ ጋር ትቀላቀላለህ ... " በማለት ስለአታለሉት ነው፤ የሚል ወሬ በያለበት በተለይም በምድረ ጐጃም በሰፊው መወራቱን ዊልፍሬድ ቴሲገር "የመረጥኩት ሕይወት" (The Life of My Choice) በተባለው መጽሐፉ ውስጥ ገልጾታል። አርድ ዊንጌትም በልዩ ማስታወሻው ላይ በግልጽ አስፍሮታል። ይሁን እንጂ፤ የበላይ ዘለቀን ከራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት ጋር መተባበርና ለጠላት ጦር ረዳት ሆኖ መገኘት፤ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ "ሕይወቴና የኢትዮጵያ እርምጃ" በተሰኘው መጽሐፍና እንዲሁም በደጃዝማች ከበደ ተሰማ የታሪክ ማስታወሻ ውስጥ ጨርሶ አልተጠቀሰም።

እንግዲህ፤ በደብረማርቆስ በብዛት ሠፍሮ የነበረው የጠላት ጦር፤ የተወሰኑ መሣሪያዎቹን ለባንዳው ለራስ ኃይሉ ተክለሐይማኖት አስረክቦ አባይን ከተሻገረ በኋላ፤ ወደየትኛው አቅጣጫ ማምራት እንደሚችል አያውቅም ነበር። በዚያን ጊዜ አዲስ አበባ በጄኔራል ካኒንግሐም ጦር ለመያዝ ተቃርባለች፤ ደሴም ተይዟል። በጐንደር ከሚገኘው ከናዚ ጦር ጋር ለመቀላቀልም በያለበት ያሉት የኢትዮጵያ አርበኞች እየተጠናከሩ መንገዶቹን ሁሉ ስለዘጉበት፤ መንቀሳቀስ አልቻለም። ስለዚህ፤ የማራቪንታና የፋሽስት ሠራዊት ሳይወድ በግድ ፍቼ ላይ ተከታትሎ ለደረሰበት ለጌዴዎን ጦርና ለጀግኖቹ ለኢትዮጵያ አርበኞች፤ እጁን ሰጥቶ ምርኮኛ ከመሆን በስተቀር ሌላ ዕድል ሳያገኝ ቀረ።

## ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በደብረማርቆስ

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት እ.ኢ.ት.አቆ ጥር 12 ቀን 1933 ዓ.ም፤ ከካርቱም ተነሥተው "አሜድላ" በተባለው የጐጃም ግዛት የነፃነት አብሣሪ የሆነውን ባንዲራችንን ካውለበለቡ በኋላ፤ ከጠላት ጋር እየተዋጉ ደብረማርቆስ ለመድረስ ሰባ ስድስት ቀናት (76) ፈጅቶባቸዋል። መጋቢት 28 ቀን 1933 ዓ.ም እሁድ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በጌዴዎን ጦርና በአርበኞቻቸው ታጅበው ከጐጃም ዋና ከተማ ደብረማርቆስ ሲገቡ፤ ከኬንያ ተነሥቶ በደቡብ ኢትዮጵያ በኩል የዘመተው የጀኔራል ካኒንግሃም ጦር ሞቃዲሾንና ሐረርን በእጁ ካደረገ በኋላ፤ በዚሁ በመጋቢት 28 ዕለት አዲስ አበባን ያዘ። ንጉሠ ነገሥቱም ይህንን ዜና እንደሰሙ ፤ ወዲያውኑ በመናገሻ ከተማቸው ለመገኘት ስለቆረጡ፤ የአውሮፕላን መጓጓዣ እንዲሰጣቸው የጠየቁትን የእንግሊዝ የጦር ባለሥልጣኖች ሳይስማሙበት ቀሩ።




የነፃነቱን የዘመቻ ጉዞ ከካርቱም እና ከኬኒያ እስከ አዲስ አበባ የሚያሳየውን
ይህን ከዚህ በላይ ያለውን ካርታ ያዘጋጁት፤ ከአዲስ አበባ ዩኒቨርሲቲ
አቶ ተሰማ በቀለ ናቸው፤

ለዚህም እምቢታ እንግሊዞቹ የሰጡት ምክንያት፣ በአዲስ አበባ ያሉትን በብዙ ሺህ የሚቆጠሩትን ጣልያኖች፣ ከጃንሆይ ጋር የሚመጡት አርበኞች በደም ፍላት ተነሳሥተው ሊጨርሷቸው ስለሚችሉ፣ ፀጥታው ተረጋግቶ እነሱም አገሩን ለቅቀው እስኪወጡ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ደብረማርቆስ መቆየት ይኖርባቸዋል የሚል ነው። ይህ የእንግሊዞች ሥጋት መሠረት የሌለው መሆኑን ያልተገነዘበ የለም። የእነ ካኒንግሐም ዓላማ፣ አዲስ አበባን በሚገባ ለመያዝና በየመስኩ የራሳቸውን አስተዳደር ለመዘርጋት፣ ከዚያም በላይ የፋሽስት መንግሥት ትቷቸው የሸሸውን ንብረቶች በሙሉ እየዘረፉ ወደ ኬንያ ለማሻገር እንዲመቻቸው መሆኑ ኋላ በግልጽ ታውቆባቸዋል።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አዲስ አበባ እንዳይገቡ እንግሊዞች ባደረጉት ውሳኔ እጅግ ቢያዝኑም፣ በትዕግሥት ከመጠበቅ በስተቀር ለጊዜው ከእነሱ ጋር መጋጨቱን አልፈለጉም። የኢትዮጵያና የጃንሆይ ወዳጆች የሆኑት ሳንድፎርድና ዊንጌት በጣም ተቆጭተው፣ በተለይ ዊንጌት የካኒንግሐምን ትዕዛዝ አንቀበልም ብለን ጉዞአችንን ወደ አዲስ አበባ እናምራ ብሎ ነበር። እዚህ ላይ የሚያስደንቀው፣ የዊንጌትን ንዴት ለማብረድና በትዕግሥት እናሳልፈው እያሉ ዋና መካሪ የሆኑት ጃንሆይ ራሳቸው ነበሩ። በእውነትም በዚያ አስቸጋሪ ሰዓት ከእንግሊዞቹ ጋር በመግባባት መንፈስ ካልሆነ በስተቀር፣ በጠብ ጉዳና የሚፈጸም ነገር አልነበረም። ስለዚህ፣ ጃንሆይ ጉዳዩን በትዕግሥት ይዘን ወደ አዲስ አበባ የምንገዝበትን መንገድ በእርጋታ እናደራጅ ብለው መምከራቸው ጥሩ ዘዴ መሆኑ በመጨረሻው ውጤት ታይቷል።

የእንግሊዝ የጦር ባለሥልጣኖች በወሰኑት መሠረት፣ ንጉሠ ነገሥቱ በደብረማርቆስ በቆዩባቸው በሦስት ሳምንታት ውስጥ፣ በመላ ጐጃም በልዩ ልዩ ሥፍራዎች ከጠላት ጋር ሲዋጉ የኖሩትን ዋና ዋናዎቹን አርበኞች እነ ልጅ ዮሐንስ እያሱን፣ እነ ልጅ ኃይሉ በለውንና እነ ልጅ በላይ ዘለቀን አንድ በአንድ እየተቀበሉ በማነጋገር፣ ጠላትን በባንዳነት ሲረዱ ለኖሩት ለራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖትና ለመሰሎቻቸውም ምሕረት በመስጠት፣ ከዚያም ወደ አዲስ አበባ የሚያደርጉትን ጉዞ በምን መልክ ማዘጋጀት እንደሚያስፈልግ ሲሠሩ ሰንብተዋል። በዚያን ሰዓት የነበረው ጠቅላላ ሁኔታ እንደሚያመለክተው፣ በሰሜን ኤርትራ በኩል የዘመተው የጄኔራል ዊሊያም ፕላት ጦር፣ እ.ኢ.ት፣አቆ በመጋቢት 23 ቀን 1933 ዓ.ም አሥመራን ይዞ ምፅዋን ከተቆጣጠረ በኋላ፣ የፋሽስቱ የዱካ ዳ አስታ አልሞት ባይ ሠራዊት ወደመሸገበት ወደ አምባ-አላጌ አምርቷል። በኬንያ በኩል የተሰለፈውም የጄኔራል ካኒንግሃም ጦር፣ ቀደም ሲል እንደተገለጸው ሞቃዲሾን፣ አጋዴንና ሐረርጌን በእጁ አድርጐ አዲስ አበባን ከያዘ በኋላ፣ በያለበት በሽሽት ላይ የሚገኘው የፋሽስት ሠራዊት ተይዞ ምርኮኛ ከመሆን በስተቀር ሌላ ዕድል እንደማይኖረው የታወቀ ነበር።

ከካርቱም ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ይዞ በጐጃም ክፍለ ሀገር በአሜድላ፣ በበላያና በቡሬ እየሠፈረ፣ ጠላትን እየወጋና እያባረረ ደብረማርቆስ ለመግባት የበቃው የጌዴዎን ጦር፣ ሸሽቶ አባይን የተሻገረውን የፋሽስቱን የኮሎኔል ማራቪንታኖን ሠራዊት ተከታትሎ ሰላሌ ላይ ለመማረክ በመቻሉ፣ ከፍተኛ የሆነውን ድል ለመጐናጸፍ በቅቷል። ንጉሠ ነገሥቱ ከደብረማርቆስ ተነሥተው ወደ አዲስ አበባ በጀመሩት ጉዞ በሰላሌ አውራጃ ፍቼ ከተማ ሲደርሱ፣ በጌዴዎን ጦር ኃይልና በአርበኞቻቸው ተሳትፎ የተማረከውን የጠላት ሠራዊት ለመጐብኘት መፈለጋቸውን ለዊንጌት አስታወቁት። ዊንጌትም በበኩሉ የጃንሆይ ጥያቄ በሚገባ



የጌዴዎን ጦር ዋና አዛዥ ሜጀር ዊንጌት፤ ለኢትዮጵያ ዘመቻ ያቀደውን ፕላን ለንጉሠ ነገሥቱ ሲያስረዳ፤

እንዲፈጸም ለረዳቱ መኰንን ለዊልፍሬድ ቴሲገር ትዕዛዝ ሰጠ። የሰልፉ ዝግጅት ሲጀመር፣ የምርኮኞቹ መሪ ኮሎኔል ማራቪንታኖ፣ ይህ ዓይነቱ አሠራር ከሰብዓዊ ሥልጣኔ መንገድ ውጭ ፍጹም የሆነ የአረመኔነትን ተግባር የሚያሳይ ነው በማለት፣ ተቃውሞውን ገለጸ። ቴሲገር ወዲያውኑ መለሰለት።

" ... በአንተ ትርጉም አረመኔነት ምን ማለት ነው? ... እናንተስ እስከ ዛሬ ድረስ በኢትዮጵያ ላይ ስትፈጽሙት የኖራችሁት የአረመኔነትን ተግባር አይደለም ወይ? ... የናንተ ጥቁር ሸሚዝ ለባሽ የሆኑት ፋሽስቶች፣ በአዲስ አበባ ከተማ ብቻ ስንቱን ሺህ ሕዝብ ነው በግራዚያኒ ትዕዛዝ ያለ አንዳች ርኅራኄ የጨፈጨፉት? የናንተ አረመኔዎች የሆኑት ወታደሮች አይደሉም ወይ? ደብረሊባኖስ ገዳም ገብተው፣ እነዚያን አራት መቶ የሚሆኑ መነኮሳቶችና መናኒያኖች መኖሪያቸውን በእሳት እያቃጠሉ በመትረየስ የፈጅዋቸው? እናንተ አይደላችሁም የንጉሡ ነገሥቱን አማች ራስ ደስታ ዳምጠውንና ሁለቱን የራስ ካሣ ልጆች፣ ደጃዝማች አበራና ደጃዝማች የወንድወሰን ድል መሆናቸውን ተቀብለው እጃቸውን ከሰጡ በኋላ መላው ዓለም ከሚከተለው ሕግ ውጭ በሚያሰቅቅ ሁኔታ የገደላችኋቸው? ... ታዲያስ! ይህ ሁሉ ሥራችሁ ፍጹም የሆነ የዓረመኔ ተግባር አይደለም? አሁን እኛ ተዋግተን የማረክናችሁን ፋሽስቶች፣ ንጉሠ ነገሥቱ እንዲጐበኟችሁ ስናደርግ፣ በዓለም ሕግ የተፈቀደውን ከመፈጸም በስተቀር ምኑ ነው የዓረመኔ ሥራ መስሎ የታያችሁ? የዛሬ አምስት ዓመታት ገደማ የኢትዮጵያን ዋና ከተማ አዲስ አበባን ከያዛችሁ በኋላ፣ ሰላማዊውን የአገሩን ሕዝብ አንገቱንና እግሮቹን እየቆራረጣችሁ መቀጣጫ ይሁን ብላችሁ ያዘጋጃችሁትን የፎቶግራፎች ኤግዚቢሽን ከጥቂት ቀናት በፊት አይቼ፣ ሠልጥናችኋል በመባል አጉል ዝና በተሰጣችሁ በእናንተ ጣልያኖች ምን ያህል እጅግ አድርጌ እንዳዘንኩ ሳልነግራችሁ ማለፍ አልፈልግም። በተጨማሪም ምናልባት አንተው ራስህ ኮሎኔል ማራቪንታኖ ሮም ተገኝተህ በዓይንህ አይተህ ይሆናል። ኢትዮጵያን በጦር ኃይል ወግተን ይዘናታል ካላችሁ በኋላ፣ ኢትዮጵያውያን ምርኮኞችን ሮም ወስዳችሁ፣ እንዴት በመሰለ ግፍ እያሰቃያችሁ ለጌታችሁ ለሙሶሊኒ በአደባባይ ላይ እንዳቀረባችኋቸው አይቶ ያላዘነና ያልተሳቀቀ የለም። እንደእውነቱ ከሆነ፣ አሁን እናንተ ደግሞ በተራችሁ ይህን ዓይነቱን ግፍ ልትቀምሱት በተገባ ነበር። ነገር ግን እኛ እንደ እናንተ የዓረመኔን ተግባር አናከናውንም። ነገ ከጠዋቱ በአራት ሰዓት በአንተ በኮሎኔል ማራቪንታኖ ቀዳሚነት እጃችን የገባችሁት የፋሽስት ምርኮኞች በሙሉ በንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ፊት በሰልፍ እያለፋችሁ እንድትታዩ ይደረጋል። ይህንን በደስታ ተቀብላችሁ ካልፈጸማችሁ፣ በሰላሌ ተዘጋጅቶ የሚጠባበቀውን የራስ ካሣን ጦር ጠርቼ አስረክባችኋለሁ። በዚህ ጊዜ ምን እንደሚደርስባችሁ እኔ አላውቅም። ማወቅም የለብኝም። ምርጫው የእናንተ ነው ... "

ከዚህ በላይ የተገለጸውን ቃል እንግሊዛዊው መኰንን ቴሲገር ሲናገር፣ ኮሎኔል ማራቪንታኖ እየተንቀጠቀጠ አሜን ብሉ ከመቀበል በስተቀር ምንም ማለት አልቻለም ነበር። ቴሲገር እንደወሰነው፣ በጠዋቱ በአራት ሰዓት ምርኮኞቹ ሰልፉ ወደተዘጋጀበት ቦታ ተወስደው፣ ለንጉሠ ነገሥቱ የክብር ሰላምታ እያቀረቡ ሲያልፉ፣ ግራና ቀኙን የተሰለፈው ሕዝብ በጩኸትና በእልልታ የሚገልጸው ደስታ፣ አርበኞቹ የሚያሰሙት ፉከራና ሽለላ፣ ለፍቼ ከተማ ልዩ የሆነ ድምቀት ሰጥቷት ነበር። ልዑል ራስ ካሣ ከንጉሠ ነገሥቱ በቀኝ በኩል ቆመው፣ የምርኮኞቹን ሠልፍ ሲመለከቱ፣ ፋሽስቶች በጭካኔ የገደሏቸው ልጆቻቸውን ደጃዝማች አበራንና ደጃዝማች ወንድወሰንን በማሰብ የተሰማቸው ሐዘን ምን ያህል

የመረረ እንደሆነ ይታይ ነበር። ራስ ካሣ፣ " ... ክፉ ለሠራብህ ክፉ አትዋልለት ... " የተባለውን የፈጣሪ ቃል በሙሉ ዕምነት የሚከተሉ የዚህንም ዓለም ከንቱነትና ጊዜያዊነት ተገንዝበው ገና በአፍላው ዕድሜያቸው የተለዩት በመሆናቸው፣ ኃዘናቸውን በኢትዮጵያ ደስታ ለውጠው፣ የልጆቻቸው ደመኞች የሆኑት እነ ኮሉኔል ማራሺንታኖ ብድሩ ሊደርሳቸው ይገባል ብለው አላስቸገሩም። ራስ ካሣ፣ በዚያን ጊዜ የሰላሌ ግዛትና ሕዝቡ የእሳቸው ስለሆነ፣ እሳቸው ከፈለጉ በልጆቻቸው ላይ ለተሠራው ግፍ አጸፋውን ለመመለስ ኃይሉም ድርጅቱም የሚያንሳቸው አልነበረም። ነገር ግን ስለምርኮኞች አያያዝ በዓለም ላይ የሚሠራበትን ሰብዓዊነት በማሰብ፣ የኢትዮጵያንም ክብርና ዝና ለመጠበቅ፣ በፋሽስቶቹ ጠላቶቻችን ላይ ምንም ነገር እንዳይደርስባቸው ንጉሠ ነገሥቱ የወሰኑትን ሁሉ ለመቀበልና ለመፈጸም፣ የወንድም ጓደኛቸው ራስ ካሣ አላመነቱም።

## ከፍቼ ወደ አዲስ አበባ

ሁለት መቶ ሰማንያ ሁለት መኮንኖችና አሥራ አምስት ሺህ የፋሽስት ወታደሮች፣ በጌዴዎን ጦር ኃይልና በኢትዮጵያ አርበኞች ጀግንነት መማረካቸውን ንጉሠ ነገሥቱ በሥፍራው ተገኝተው በጉበኙ ጊዜ፣ የእግዚአብሔርን ተአምር በማሰብ ምን ያህል ደስታ እንደአደረባቸው ለመገመት የሚቻል አልነበረም። መራራውን የስደት ሕይወት ከእንግሊዝ አገር ከለቀቁበትና ካርቱም ከደረሱበት ካለፉት አሥር ወራቶች ጀምሮ፣ በሱዳንና በጉጃም አውራጃዎች እየተዘዋወሩ ለነፃነቱ ትግል ምን ያህል እንደተሰቃዩና ምን ያህል እንደደከሙ ዝርዝሩን ለተመለከተው የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ጥንካሬና ቆራጥነት ለመገንዘብ አያዳግትም። ያላቸው ሰፊ ትዕግሥት ምንጊዜም የማይለያቸው በመሆኑ፣ በየጊዜው የሚደርስባቸውን መከራና ፈተና ለመቋቋም አስችሏቸዋል።

በኢት.አቆ. መጋቢት 28 ቀን 1933 ዓ.ም ከጉጃም ዋና ከተማ ደብረማርቆስ ገብተው፣ በሕዝባቸውና በአርበኞቻቸው መካከል የኢትዮጵያን ሰንደቅ ዓላማ በማውለብለብ ወሰን የሌለው ደስታቸውን በሚገልጡበት ሰዓት፣ ወደ መናገሻ ከተማቸው ወደ አዲስ አበባ በቶሎ እንዳይገቡ የእንግሊዙ ጦር አዛዥ የጄኔራል ካኒንግሐም ውሳኔ ሲደርሳቸው፣ ከዚህ የበለጠ ምራልን የሚነካ ብስጭት ሊደርስባቸው አይችልም በማለት፣ በዙሪያቸው ያሉት ረዳቶቻቸው በሙሉ እጅግ አዝነውና ተጨንቀው ነበር። <u>እሳቸው ግን የእንግሊዞቹን ውሳኔ ከምንም አልቆጠሩትም</u>። ከእኛ ቀድመው መናገሻ ከተማችንን የያዙት የታላቋ ብሪታንያ የጦር አለቆች የእኛን መቆየት የሚፈልጉት፣ ለእኛ ለሚደረገው አቀባበል ዝግጅት እንዲመቻቸው ከሆነ፣ ማለፊያ ነው፣ እነሱም ይዘጋጁ፣ እኛም እንዘጋጃለን ብለው፣ ሥራቸውን ቀጠሉ። ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ በካኒንግሐም ውሳኔ እጅግ የተበሳጨውንና ትዕዛዙን መቀበል የለብንም ብሉ የተነሣውን አርድ ዊንጌትን በማጽናናትና በመምከር ንዴቱን ያስታገሡለት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ናቸው። ከዚህም በመቀጠል፣ በንጉሠ ነገሥትነታችን አዲስ አበባ ስንገባ ለሚደረግልን አቀባበል ዝግጅት፣ ከጄኔራል ካኒንግሐም ጋር እንዲሠሩ በማለት፣ ስድስት ሰዎች መርጠው ላኳቸው። እነዚህም፣

- ደጃዝማች መኰንን እንዳልካቸው (ኋላ ራስ ቢትወደድ)
- ሻለቃ አቢይ አበበ (ኋላ ሌ.ጄኔራል)
- ሻለቃ ሙሉጌታ ቡሊ (ኋላ ሜ.ጄኔራል)

- ሻለቃ ነጋ ኃይለሥላሴ (ኋላ ሌ. ጄኔራል)
- ሻለቃ ከበደ ገብሬ (ኋላ ሌ.ጄኔራል)
- ልጅ አስፋው ከበደ (ኋላ ፊታውራሪ) ነበሩ።

የእነ ጄኔራል ካኒንግሐም ፍላጐት፣ ንጉሠ ነገሥቱ አዲስ አበባ የሚገቡት በደብረማርቆስ ቢያንስ ሁለት ወራት ያህል ከቆዩ በኋላ እንዲሆን ነበር። ቀደም ሲል እንደተነገረውም፣ እንግሊዞቹ በንጉሠ ነገሥቱ ላይ ይህንን ዕገዳ ያደረጉት፣ ጃንሆይ ከመግባታቸው በፊት ሥልጣናቸውን በሰፊው አስፋፍቶ ለመያዝና፣ ከዚህም በላይ የጠላት ንብረት የሆኑትን ዕቃዎች ሁሉ እየለቀሙ በኬንያ በኩል ለማሻገር እንዲመቻቸው መሆኑ ታውቋል። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ግን፣ ምንም እንኳን በዚያን ሰዓት ከእንግሊዞቹ ጋር መጋጨት አይጠቅምም ብለው የካንኒግሐምን ውሳኔ ለጊዜው በትዕግሥት ቢያልፉትም፣ ከሦስት ሳምንታት በላይ በደብረማርቆስ መንገዱ ተዘግቶባቸው መቀመጥን አልፈለጉም። አማካሪያቸውና የጦር መሪያቸው ኦርድ ዊንጌትም፣ በጃንሆይ ሐሳብ የሚስማማ በመሆኑ፣ እሱም በበኩሉ ለሦስት ሳምንታት ያህል ከታገሠ በኋላ፣ የካኒንግሐምን ትዕዛዝ ለመጣስና የንጉሠ ነገሥቱን የአዲስ አበባ ጉዞ ለማፋጠን እርምጃ ወሰደ። ከደብረማርቆስ እስከ ሰላሌ አውራጃ በተደረገው ጉዞ ላይ፣ ዊንጌት መልካም አጋጣሚ የሆነ ዕድል ስለቀናው፣ በኮሎኔል ማራቬንታኖ የሚመራውን አሥራ አምስት ሺህ (15.000) የጠላት ጦር ማርኮ፣ ንጉሠ ነገሥቱ በከፍተኛ ሥነ ሥርዓት ምርኮኞቹን እንዲቀበሉ በማስደረጉ፣ እነ ጄኔራል ካኒንግሐም በቅናት ተበሳጩ። ነገር ግን፣ ኦርድ ዊንጌት ስለ ጄኔራል ካኒንግሐም ቁጣ ወይም ቅሬታ፣ ቁም ነገር አልሰጠውም። ጃንሆይ ወደ መናገሻ ከተማቸው የሚገቡበት ቀን እንዲዘገይ የተላለፈለትን ትዕዛዝ አሻፈረኝ ብሎ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከፍቼ ከተማ እንደ ኢት.አቆ. ሚያዝያ 27 ቀን 1933 ዓ.ም (05/05/41) በጠዋት ተነሥተው በዚሁ ዕለት አዲስ አበባ እንዲገቡ መወሰኑን አስታወቀ። ይህንን ውሳኔ ለማገድ ካኒንግሐም አልቻለም። አንዳንዶቹም ባንዶች የአዲስ አበባን መግቢያ በር በወታደሮች ዘግቶ ንጉሠ ነገሥቱ ለጥቂት ቀናት እንጦጦ እንዲቆዩ ማድረግ ይቻላል የሚል ምክር አቅርበውለት እንደነበረ ይነገራል። ካኒንግሐም ግን፣ እስከዚህ የንጉሠ ነገሥቱን ክብር ለመዳፈር አልቃጣም። ይህንን ቢያደርግ፣ ሕዝቡ እንደሚነሣበትና መዘዙም ቀላል አለመሆኑን ስለተረዳው፣ በአጭር ጊዜ ውስጥ ለጃንሆይ አቀባበል የሚያስፈልገውን ዝግጅት ማድረግ ግዴታ ሆነበት።

በዚሁ በሚያዝያ 27 ቀን 1933 ዓ.ም ጠዋት (05/05/41) ንጉሠ ነገሥቱ በጌዴዎን ጦር ታጅበው ከፍቼ ተነሥተው እንጦጦ ማርያም በር ላይ ሲደርሱ፣ ሌሊቱን ሙሉ ሲሰናዱ ያደሩት ስመ ጥሩው ጀግና ራስ አበበ አረጋይ ቁጥራቸው ወደ አሥር ሺህ የሚጠጉትን የአርበኞች ሠራዊታቸውን አሰልፈው እጅግ የደመቀና የጋለ አቀባበል አደረጉላቸው። በአገር ፍቅር እሳት እየነደዱ፣ አምስቱን ዓመታት ሳያቋርጡ ከጠላት ጋር ሲዋጉና ጠላትን ሲያስጨንቁ የኖሩት ጀግናው አበበ አረጋይ፣ በእነዚህ በመከራዎቹ ዘመናት ከንጉሠ ነገሥታቸው ጋር በደብዳቤ ከመጻጻፍ በስተቀር፣ በዓይነ ሥጋ ሳይተያዩ የኖሩ በመሆናቸው፣ እንጦጦ ላይ ለመጀመሪያ ጊዜ ሲገናኙ፣ በመካከላቸው ሲገለጽ የታየውን የደስታ ስሜትና እጅግ የጋለ መንፈስ መለካት የሚቻል አልነበረም። በኢት.አቆ. ነሐሴ 14 ቀን 1896 ዓ.ም ወደዚህ ዓለም የመጡት አበበ አረጋይ፣ አባታቸው የፍርድ ሚኒስትር የነበሩት አፈንጉሥ አረጋይ በቸሬ ሲሆኑ፣ እናታቸው የራስ ጉበና ዳጬ ልጅ ወይዘሮ አስካለማርያም ጉበና ናቸው። በወግ ያደጉና የአገር ባሕል ሥርዓትን የተማሩ፣ የኢትዮጵያን መሠረታዊ አቋምና የተከበረ ታሪኳን ጠንቅቀው የሚያውቁ፣

በብልህነታቸውና እርጋታ በተመላበት መልካም ጠባያቸው፤ ለሚወዷት አገራቸው ምንጊዜም ሲደነቅና ሲታሰብ የሚኖረውን ፍሬያማ አገልግሎት ያበረከቱ ታላቅ ሰው ናቸው። በአገራችን ላይ በወደቀው የመከራ ዘመን ለነፃነታችን ባደረጉት ትግል፤ የገነቡትን ከፍተኛ ዝና፤ ያተረፉትን ከፍተኛ ክብር፤ ያስገኙትን ከፍተኛ ድል፤ የኢትዮጵያችን ታሪክ እጅግ የተከበረውን ሥፍራ ሰጥቶ ሲያስታውሳቸው የሚኖር ነው።

ቀኛማቺ ኃይለሥላሴ እንጦጦ ሲደርሱ ራስ አበበ አረጋይና ሠራዊታቸው የደመቀ አቀባበል ካደረጉላቸው በኋላ፤ አርድ ዊንጌት ባዘጋጀው የጉዞ ፕላን፤ ንጉሠ ነገሥቱ በነጭ ዳግላ ፈረስ ላይ ሆነው፤ በጌዴዎን ጦርና በኢትዮጵያ አርበኞች ታጅበው ከመናገሻው ከተማቸው እንዲገቡ ነበር። ጃንሆይ ግን፤ በተዘጋጀው ነጭ ፈረስ ላይ ተቀምጦ ጉዞውን የሚመራው እሱ ራሱ ኮሎኔል አርድ ዊንጌት እንዲሆንና እሳቸው በአርበኞቻቸውና በጌዴዎን ጦር መካከል በግልጽ አውቶሞቢል እየተጓዙ፤ ከእንጦጦ አዲስ አበባ ለመግባት የሚሻል መስሎ ታያቸው። ንጉሣዊው ጉዞ በዚህ ጃንሆይ በፈቀዱት መልክ እንዲሆን ከተወሰነ በኋላ፤ በጄኔራል ካኒንግሐም በኩል ደግሞ በሞተር ቢስክሌቶችና በቀላል ታንኮች ላይ ሆነው ንጉሠ ነገሥቱን የሚያጅቡ የደቡብ አፍሪካ ወታደሮች ከፖሊስ ሠራዊት ፈረሰኞች ጋር ወደ እንጦጦ ተልከው መጥተዋል። የጉዞው ዝግጅት ከዚህ በላይ በተገለጸው አኳኋን በመጠናቀቅ ላይ እንዳለ፤ ከጄኔራል ካኒንግሐም የተላከ ለዊንጌት አንድ መልዕክት ደረሰ። መልዕክቱም፤ " ... ቁጥራቸው ከአሥር ሺህ በላይ የሚገመተው በራስ አበበ አረጋይ የሚመሩት አርበኞች፤ ንጉሠ ነገሥቱን አጅበው ወደ አዲስ አበባ ከመምጣት ለአርባ ስምንት ሰዓቶች ያህል እዚያው ለሉበት እንጦጦ ሠፍረው እንዲቆዩ ... " የሚጠይቅ ነበር። ዊንጌት በዚያን ጊዜ ከጃንሆይ አጠገብ ከነበሩት መካከል አርበኛው አቶ ጌታሁን ተሰማን እንዲያስተረጉሙለት ጠይቆ፤ የካኒንግሐምን ሐሳብ ለራስ አበበ ነገራቸው። ራስ አበበ መልዕክቱን እንደሰሙ፤ መልሳቸው "አልቀበልም" የሚል የጠነከረ ቃል ነበር። ምክንያታቸውንም እንደሚከተለው አስረዱ። " ... ንጉሠ ነገሥታችን በአገራችን በኢትዮጵያ ላይ የፋሽስት መንግሥት የሚፈጽመውን ግፍ ለዓለም መንግሥታት ማህበር ለማመልከት ወደ አውሮፓ ሲሄዱ፤ እኛም አገልጋይዎቻቸው አዲስ አበባን ለቅቀን በየጫካውና በየገደሉ በመሠማራት፤ ከጠላታችን ጋር ለነፃነታችን ስንዋጋ አምስቱን ዓመታት አሳልፈናል። ዛሬ የእግዚአብሔር ፈቃድ ሆኖ የወዳጅ አገር የእንግሊዝም መንግሥት እርዳታ ተጨምሮበት፤ ንጉሠ ነገሥታችን የነፃነታችንን ችቦ እያበሩ ወደ መናገሻ ከተማቸው ሲያመሩ፤ እኛ ተነጥለን እዚህ እንጦጦ እንድንቆይ የምንጠየቀውን አንቀበልም። አሁን የቆምነው ነፃ በሆነችው በአገራችን መሬት ላይ ነው። ዛሬም ለመጓዝ የተዘጋጀነው ነፃ ወደሆነችው ወደ አዲስ አበባ ከተማችን ነው። ምናልባት የአዲስ አበባ ፀጥታ አሥግቷችሁ እንደሆነ፤ እኛ በቂ የሆነ ኃይል ስላለን፤ በቶሎ ደርሰን እንጋፈጥላችኋለን። ከዚህ ሌላ ባታስቸግሩን ይሻላል። እኛ ውለታችሁን ማሰብ፤ እናንተም ምስጋናችንን መቀበል የሚገባ ነው። ከዚህም ውጭ የምንጠይቃችሁ የለም ... "

ዊንጌት ፈነደቀ። በራስ አበበ መልስ እጅግ ተማረከ። ወዲያውኑ ለካኒንግሐም ባስተላለፈው ቃል፤ " ... የታወቀው ጀግና የአርበኞች መሪ አበበ አረጋይ፤ ከጃንሆይ ተለይተን እንጦጦ ለመቆየት ጨርሶ የማይታሰብ ነው ብሏል። የንጉሠ ነገሥቱም አቋም ይህንኑ የመሰለ ስለሆነ፤ ሐሳቡን ከመቀበል በስተቀር ምርጫ የለም ... " ሲል አስታወቀ። ካኒንግሐም ሌላ ታሪክ መፍጠር አልፈለገም። በፕሮግራሙ መሠረት ሚያዝያ 27 ቀን 1933 ዓ.ም ንጉሠ ነገሥቱ በከፍተኛ አጀብ እኩለ ቀን ስድስት ሰዓት ላይ ከታላቁ የዳግማዊ ምኒልክ ቤተመንግሥት

አደባባይ ላይ ሲደርሱ፤ የክብር ዘብ አሰልፎ ዋና ዋናዎቹን የጦር አለቆች ይዞ የደስታ መግለጫ መድፍ እያስተኮሰ በመልካም ሥነ ሥርዓት ተቀበላቸው። እ.ኢ.ት፤አቆ. ሚያዝያ 27 ቀን 1928 ዓ.ም በዚህ በታላቁ የዳግማዊ ምኒልክ ቤተመንግሥት አደባባይ ላይ የፋሽስትን ድል በማብሠር ማርሻል ባዶሊዮ የኢትዮጵያን ሰንደቅ ዓላማ አስወርዶ የጣልያንን ባንዲራ የሰቀለበት ቀን ነበር። ልክ በአምስተኛ ዓመቱ ደግሞ ሚያዝያ 27 ቀን 1933 ዓ.ም ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በዚያው ቦታ አረንጓዴ፣ ቢጫ፣ ቀይ የሆነውን ባንዲራችንን መልሰው ሰቅለው ሲያውለበልቡ፤ ከእንግዲህ ወዲህ የኢትዮጵያ ሕዝብ ነፃነት ለዘለዓለሙ የማይነካ መሆኑን አረጋገጡ።

## ይህች ቀን ለአዲሲቷ ኢትዮጵያ
## የአዲስ ታሪክ ዘመን መክፈቻ ነች፤

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ያንን ሁሉ የመከራና የፈተና ዘመን አሳልፈው፤ የኢትዮጵያን ነፃነት ይዘው ከመናገሻ ከተማቸው ሲገቡ፤ ለፈጣሪዬ ምጋናዬን በምን ቃል ባቀርብለት ይሰማኝ ይሆን? ለሕዝቤስ በምን ቃል ብነግረው ልባዊ ስሜቴን ይረዳልኝ ይሆን? እያሉ በመንገዳቸው ላይ ሲያስቡበትና ሲጨነቁበት እንደነበረ፤ አጠገባቸው የነበሩት ረዳቶቻቸው ሁሉ ያስታውሳሉ።

> አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤
> የጃንሆይ ልዩ ረዳትና የጽሕፈት ቤታቸው ሹም፤
> አቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝ፤
> የጃንሆይ የፖለቲካ አማካሪ፤
> አቶ ጌታሁን ተሰማ፤
> በጉጃም የአምስት ዓመት አርበኛ፤

ንጉሠ ነገሥቱ አዲስ አበባ ሲገቡ፤ ለኢትዮጵያ ሕዝብና ለመላው ዓለም የሚያሰሙትን ንግግር እንዲያዘጋጁ ታዘው ነበር። ይህ ልዩ ኮሚቴ፤ ከደብረማርቆስ እስከ አዲስ አበባ በተደረገው ጉዞ ላይ አመቺ ጊዜ ሲያገኝ እየተሰበሰበ በማጥናትና የንጉሠ ነገሥቱንም መምሪያ በመቀበል ባዘጋጀው ዲስኩር ውስጥ፤ ጃንሆይ የተናገሯቸው ዋና ዋናዎቹ ሐሳቦች የሚከተሉት ናቸው።

## የአገሬ የኢትዮጵያ ሕዝብ ሆይ!

> የሰማይ መላዕክት፤ የምድር ሠራዊት ሊያስቡትና ሊያውቁት ይቻላቸው ባልነበረ በዚህ በዛሬው ቀን፤ ቸሩ እግዚአብሔር በመካከላችሁ ለመገኘት ስለአበቃኝ፤ በሰው አፍ ተነግሮ የሚበቃ ምስጋና የለኝም።
> ዛሬ ኢትዮጵያ እጆችዋን ወደ እግዚአብሐር ዘርግታ ዕልል እያለች ምስጋናዋን የምታቀርብበት፤ ፍጹም ደስታዋን ለልጆቿ የምትገልጽበት፤ ልጆችዋም ከባዕድ የመከራ ቀንበርና ከባርነት አገዛዝ ነፃ የወጡበት፤ እኛም አምስት ዓመት ሙሉ ተለይተነው ከነበረው ከአገራችንና ከሕዝባችን ጋር ለመቀላቀል የበቃንበት፤ በተጨማሪም ለአገራችን ነፃነትና ለሰንደቅ ዓላማችን ክብር

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በታላቅ አጀብ መናገሻ ከተማቸው አዲስ አበባ ሲገቡ፤




በግራ በኩል የጌዴዎን አዛዥ ሜጀር ዊንጌት በነጭ ፈረስ ሆኖ ይታያል፤

መሥዋዕትነትን በመቀበል ደማቸውን ያፈሰሱትንና አጥንታቸውን የከሰከሱትን ጀግኖቻችንን የምናስታውስበት ታላቅ ቀን ስለሆነ፤ በየዓመቱ ልናስበውና ልናከብረው የሚገባ ነው።

የአገሬ የኢትዮጵያ ሕዝብና መላው ዓለም ደህና አድርጐ እንደተረዳው፤ የፋሽስት መንግሥት የአድዋን ብድር ለመመለስና ነፃነታችንን ገፍፎ ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ ዝግጅት የጀመረው፤ ከብዙ ዓመታት በፊት ነው። በተለይም በወሰናችን ላይ ጠብ እየጫረ ችግር በሚፈጥርብን ጊዜ፤ የሙሶሊኒ መንግሥት ዋና ዓላማ ኢትዮጵያን ለመውረር ምክንያት ፍለጋ መሆኑን፤ ለዓለም መንግሥታት ማህበርና ለታላላቆቹ የአውሮፓ መሪዎች ከማመልከትና ከማሳሰብ አላቋረጥንም ነበር። ይሁን እንጂ፤ አቤቱታችንን የሚዳምጥልንና በዳኝነት የሚያይልን ልናገኝ አልቻልንም። ጠላታችንም ረዳት የሌለን መሆናችንን በማየት የልብ ልብ ስለተሰማው፤ በመስከረም 1928 ዓ.ም ጦሩን አሠልፎ ወሰናችንን ጥሶ ሲወጋን፤ ባለን አቅም ሁሉ ነፃነታችንን ለመከላከል እርምጃ ወሰድን። ቀደም ሲል እንደገለጽነው፤ ጠላታችን ከብዙ ዓመታት ጀምሮ እኛን ለመውረር ያዘጋጀው የጦር ወታደርና ዘመናዊ የመሣሪያ ኃይል በብዙ መቶ ሺህ የሚቆጠር በመሆኑ፤ መላ ኢትዮጵያን ለመያዝ ከአንድ ወር የበለጠ ጊዜ የሚፈጅበት አልመሰለውም ነበር። ነገር ግን፤ አገራችን ኢትዮጵያ ምንም እንኳ ከዓለም ማህበር ዳኝነት ቢነፈጋት፤ ከወዳጅ መንግሥታት እርዳታ የሚሰጣት ብታጣ፤ በገዛ ገንዘቧ የጦር መሣሪያዎች ለመግዛት እንዳትችል ብትከለከል፤ ቀደም ሲል የገዛቻቸው መሣሪያዎችም እንዳይደርሱላት በውጭ መንግሥት ወደብ ላይ ቢታገድባት፤ ጀግኖቹ የኢትዮጵያ ልጆች የመጣባቸውን ጠላት ከመመከትና ተጋፍጠው ከመዋጋት ወደ ኋላ አላሉም። የፋሽስት ኃይል ለአምስት ወራት ያህል በሰማይ በአውሮፕላን ቦንብ፤ በመሬት በከባድ መሣሪያዎችና በታንክ ባደረጋቸው ውጊያዎች፤ ኢትዮጵያን ለመያዝ ያልቻለና የማይችል መሆኑን ሲረዳው፤ በመጨረሻው በዓለም ሕግ የተከለከለውን መርዝና ጋዝ በአውሮፕላን እየረጨ ሕዝባችንን በማቃጠልና በመጨረስ አገራችንን ለመያዝ ቻለ። ሆኖም በእነዚህ በአምስቱ ዓመታት ውስጥ የተካሄዱት ሁኔታዎች እንዳስረዱት፤ ጠላታችን የፋሽስት መንግሥት ኢትዮጵያን ከዳር እስከ ዳር ይዥታለሁ ብሎ ማስመስከርና መፎከር አልቻለም። አርበኞቻችን በዱር በገደሉ እየተዘዋወሩ በሚያደርጉት ውጊያ ጠላታችንን እንቅልፉን ነሥተው ስለአስጨነቁት፤ የሰላም ዘመን አግኝቶ አያውቅም።

ጠላታችን የኢትዮጵያ ሕዝብ በቀላሉ የሚገዛለት አለመሆኑን ሲረዳውም፤ በሕዝባችን ላይ ተወዳዳሪ የሌለውን ጭካኔና ግፍ መፈጸም ዓይነተኛ ተግባሩ አድርጐ ያዘው። ለምሳሌም ያህል 1929 ዓ.ም የየካቲት ሚካኤል ዕለት፤ በፋሽስቶች እጅ የተፈጀውን ሕዝባችንን ስናስታውስ፤ የሚዘገንነንና በኃዘን የሚያስጨንቀን ያለቀው ሕዝብ ቁጥር ብዛት ብቻ አይደለም። የአገዳደሉ ዓይነት ነው። በአካፋና በዶማ፣ በምሳርና በመዶሻ የተፈለጡትን፣ በሳንጃና በመጥረቢያ የተቆረጡትን፣ በዱላና በድንጋይ የተወገሩትን፣ በቤታቸው ውስጥ ተኝተው ከነልጆቻቸው በእሳት የተቃጠሉትን፣ በገመድ ተጠፍረው በረኃብና በውሃ ጥም ያለቁትን



ከንጉሠ ነገሥቱና ከጌዴዎን ጦር ቀድሞ አዲስ አበባ ገብቶ የጠበቃቸው ጄኔራል አለን ካኒንግሐም፤ በታላቁ ቤተመንግሥት አደባባይ ላይ ጃንሆይን ሲቀበላቸው፤



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለመላው ሕዝባቸው ንግግር ሲያደርጉ፤

ስናስታውስ፤ የሰው ልጅ በሰው እጅ ላይ ይህንን የመሰለ ጭካኔና ይህንን የሚያህል ግፍ ይፈጽማል ብለን ማሰብ ይሳነናል። የሆነ ሆኖ ይህ ሁሉ ግፍ በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ ተፈጽሞ የታዩ ስለሆነ፤ ፍርዱን ለፈጣሪያችን ከመተው በስተቀር ሌላ የምናደርገው የለም።

- ዛሬ ጠላታችን ድል ተመትቶ የወደቀበት ቀን ነው።
- ዛሬ በእግዚአብሔር ቸርነት ያገኘነው የሁላችን የደስታ ቀን ነው።
- ዛሬ ሁላችንም ደስ የሚለን በክርስቶስ መንፈስ እንጂ፤ በሌላ መሆን የለበትም።
- ለክፉ ክፉ አትመልሱ! ጠላት እንዳደረገው የጭካኔና የግፍ ሥራ አትሥሩ! የጠላታችን መወቀሻ በሆነው ነገር፤ የኢትዮጵያን መልካም ስም የሚያጐድፍ ተግባር ለመፈጸም አትሞክሩ!

የጠላታችን ዜጐች የሆኑት ሁሉ፤ በእጃቸው ያለውን መሣሪያ እያስረከቡ፤ በመጡበት መንገድ ከአገራችን እንዲወጡ እናደርጋለን።

ነፃነታችንን ለማስመለስ ከጠላታችን ጋር ሲዋጉ የነበሩትንና ዛሬም በዚህ በደስታችን ቀን ከእኛው ጋር የተሰለፉትን እንግሊዞች፤ እንደ ዘመድና ወዳጅ ተመልክታችሁ ደግነትና ቸርነት እንድታሳይዋቸው አደራ እላችኋለሁ።

በመጨረሻም ለሁላችሁም ልነግራችሁ የምፈልገው፤ ይህች የሚያዝያ 27 ቀን ለአዲሲቷ ኢትዮጵያ የአዲስ ታሪክ ዘመን መክፈቻ መሆንዋን ነው። በዚች በምንከፍታት አዲስ ዘመን፤ አገር የሚለማበትን፤ ሕዝብ የሚበለጽግበትን፤ ሥልጣኔ የሚስፋፋበትን፤ የምንሠራበትና ሕብረታችንን የምናጠነክርበት መሆኑን እንድታስቡበት አደራ እላችኋለሁ። ... በሚል ቃል ንጉሠ ነገሥቱ ለኢትዮጵያ ነፃነት ደስታቸውን የሚገልጡበትን ንግግራቸውን ደምድመዋል። ... እንደአሰቡትና እንደተመኙት ሁሉ ይህንን የአዲሱን ዘመን ሥራ ለማካሄድ ያለ አንዳች ችግር ይቻላቸው ይሆን? ... እናያለን! ...

**መረጃዎች**

1. ቀ.ኃ.ሥ ሕይወቴና የኢትዮጵያ እርምጃ
2. ደጃዝማች ከበደ ተሰማ የታሪክ ማስታወሻ
3. የኦርድ ሻርል ዊንጌት ሪፖርት
4. Wilfred Thesiger "The life of my choice" በሚል ርዕስ የጻፈው
5. Chapman-Andrews and the Emperor by Peter Leslie